# ክፍል ፯

# ያልተጠበቀው የእንግሊዞች ዘመን

# ምዕራፍ ፩

## ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከጠበቁት በላይ፤ የገነተ ልዑል ቤተመንግሥት ጉባኤ

በገኔራል ካኒንግሐም የሚመራው የእንግሊዝ የደቡብ ጦር፤ ከኬንያ ተነሥቶ የሞቃዲሾ ሱማሌንና አጋዴንን፤ ከዚያም ጅጅጋንና መላው የሐረርጌን ግዛት ከጠላት እጅ እያስለቀቀ፤ መጋቢት 28 ቀን 1933 ዓ.ም አዲስ አበባ ከገባበት ዕለት ጀምሮ የአስተዳደሩን ሥልጣን በሙሉ ያዘ። በዚህ አኳኋን ከአንድ ወር ጊዜ በኋላ ሚያዝያ 27 ቀን 1933 ዓ.ም የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በድል አድራጊነት ከመናገሻ ከተማቸው ሲገቡ፤ የጦሩ ዋና አዛዥ ገኔራል ካኒንግሐም የተቀበላቸው የአዲስ አበባንና የመላውን የአገሪቱን አስተዳደር ሥልጣን ጨብጦ ነው።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አዲስ አበባ በገቡበት ዕለት በተዘጋጀው በዓል ላይ ገኔራል ካኒንግሐም የፈለገው፤ በመጀመሪያ ንጉሠ ነገሥቱ እቢሮው ድረስ ሄደው እንዲጉበኙትና ከዚያ በኋላ አብሯቸው ሆኖ ወደ ታላቁ ቤተመንግሥት በማምራት የባንዲራው መስቀል ሥነ ሥርዓት እንዲፈጸም ነበር። እዚህ ላይ ጃንሆይ ጠነከረው፤ " ... እኔ እቢሮህ ድረስ አልመጣም። አንተው ራስህ ዳግማዊ ምኒልክ ቤተመንግሥት አደባባይ ተገኝተህ ልትቀበለኝ ይገባል* ... " ሲሉ መለሱለት። ካኒንግሐም ጥቂት ካሰበበት በኋላ፤ የንጉሠ ነገሥቱን ጥያቄ ተቀብሎ ከታላቁ ቤተመንግሥት አደባባይ ላይ በመገኘት፤ ተገቢውን የወግ አቀባበል አደረገላቸው።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ እነዚህ ኮሎኒያሊስቶች የሆኑት የእንግሊዝ የጦር አዛዦች፤ ስለወደፊቷ ኢትዮጵያ ያላቸው ምኞትና ዕቅድ፤ ከጠበቁት በላይ የሚያሳስብ ሆኖ የታያቸው፤ አዲስ አበባ ሲገቡ ገኔራል ካኒንግሐም እቢሮው ድረስ መጥተው እንዲጉበኙት ያቀረበላቸው ጥያቄ ነው። ሱዳን በቆዩበት ወራት ውስጥ፤ የእንግሊዝ የጦር መሪዎች እነ ገኔራል ዌቨልና ፕላት በመኖሪያቸውም ጉዳይ ሆነ ጦር በማዘጋጀት ረገድ ያደረሱባቸው በደል ሁሉ በቀላሉ የሚገመት አለመሆኑ ቢታወቅም፤ አሁን መናገሻ ከተማቸው ከገቡ በኋላ ደግሞ፤ ሌሎች ችግሮች ተጠምደው እንደሚቀርቡላቸው አልጠበቁም ነበር።

በዚህ በሚያዝያ 27 ቀን ለነፃነት በዓል የተዘጋጀው ፕሮግራም ተፈጽሞ፤ ንጉሠ ነገሥቱ ከገነተ ልዑል ቤተመንግሥታቸው ከገቡ በኋላ፤ ሲሆን በዚሁ ዕለት ምሽት፤ ሳይሆን ደግሞ በማግሥቱ ጠዋት ከእንግሊዞቹ ባለሥልጣኖች በተለይም ገኔራል ካኒንግሐም መጥቶ ስለ አስተዳደሩም ሆነ ስለ ጠቅላላው ሁኔታ ከጃንሆይ ጋር እንደሚነጋገር ተጠብቆ ነበር። በነዚህ በተጠቀሱት ጊዜያቶች እንኳንስ ዋናው አዛዥ ቀርቶ፤ ረዳቶቹም ገነተ ልዑል ቤተመንግሥት ድረስ መጥተው ከንጉሠ ነገሥቱ ጋር ለመነጋገር ፈቃደኞች አልሆኑም። ከሚያዝያ 27 እስከ 29 ቀን ድረስ እነ ገኔራል ካኒንግሐም ከጃንሆይ ጋር ተገናኝተው ለመነጋገር ሳይሞክሩ

* ይህን የጃንሆይን መልስ ለካኒንግሐም ያቀረቡት አቶ ጌታሁን ተሰማ ነበሩ።

በመቅረታቸው፤ ሐሙስ ሚያዝያ 30 ቀን ንጉሠ ነገሥቱ በገነተ ልዑል ቤተመንግሥታቸው ሆነው የቅርብ ረዳቶቻቸውን በመሰብሰብ፤ ምን ማድረግ ይሻላል? የሚል ውይይት አደረጉ። በዚህ ስብሰባ ላይ ተገኝተው የነበሩት የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር አቶ ጌታሁን ተሰማ ለዚህ መጽሐፍ ደራሲ የሚከተለውን አስረድተውታል። አዲስ አበባን ቀድመው የያዙት እነዚህ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት የጦር ሹማምንቶች የሚያሳዩን መንፈስ በንቀት ላይ የተመሠረተ በመሆኑ፤ እጅግ የሚያሳዝን ብቻ ሳይሆን እጅግ የሚያበሳጭም ነበር። ጃንሆይ ስብሰባችንን ሲከፍቱ፤ የሚከተለውን ንግግር አደረጉልን። " ... ሁላችሁም እንደምታውቁት፤ ከጠላታችን ከፋሽስት መንግሥት ተገላግለን ነፃነትን መለስን ብለን መደሰት ስንጀምር፤ ለነፃነታችን ረዳቶቻችን ሆነው የተዋጉልን ወዳጆቻችን እንግሊዞች፤ ባልጠበቅነው መንገድ የአገራችን አስተዳዳሪዎችና ባለሥልጣኖች ሆነውብናል። ይህንን ካለፈው አንድ ወር ጀምሮ በአዲስ አበባ ከተማችንና በሌሎቹም ግዛቶቻችን ላይ በራሳቸው ፈቃድ ያቋቋሙትን የአስተዳደር ሥልጣን፤ ለእኛ መቸ አስረክበውን እንደሚሄዱ እስካሁን አልነገሩንም። በዚህ በሦስት ቀናት ውስጥ ሁኔታውን እንደምናየው፤ በማናቸውም ጉዳይ እንግሊዞቹ ከእኛም ሆነ ከረዳቶቻችን ጋር መነጋገር አስፈላጊነቱን ያሰቡበት አይመስልም። ሁላችሁም እንደምታውቁት አዲስ አበባ በገባንበት ዕለት፤ የወዳጃችን የታላቋ ብሪታንያ ንጉሥ ጆርጅ ፮ኛ እና ጠቅላይ ሚኒስትሩ ዊንስተን ቸርችል፤ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ አንቶኒ ኤደን፤ በጠላት ግፍ ተቋርጦ ወደነበረው ወደ ንጉሠ ነገሥት ዙፋናችን በደህና በመመለሳችን ደስታቸውን በቴሌግራም ገልጠውልናል። እንግዲህ፤ የታላቋ ብሪታንያ መሪዎች ሐሳብ በዚህ አኳኋን የተገለጠ ሲሆን፤ የጦር አዛዦቹ አስተያየት ከመሪዎቻቸው የተለየ የሚሆንበት ምክንያት ምንድን ነው? ብለን ማጥናትና የምንወስደውን እርምጃ መወሰን ስለአለብን፤ እያንዳንዳችሁ ያላችሁን ሐሳብ እንድትገልጡልን እንጠይቃችኋለን ... "

ጃንሆይ ይህንን መግለጫ ሰጥተው ስብሰባውን ከከፈቱ በኋላ፤ አቶ ጌታሁን ተሰማ እንደሚያስታውሱት፤ የተናገሩት ሰዎችና ያቀረቧቸው ሐሳቦች የሚከተሉት ነበሩ።

**አቶ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፤**

> " ... እነዚህ የእንግሊዝ የጦር አዛዦች፤ ስለ ኢትዮጵያ ነፃነትና መንግሥት ስለማቋቋም ጉዳይ በጣም ግልጽ በሆነ መንገድ ባይሆንም፤ ተቃዋሚነታቸውን እንዳልሸሸጉን ጃንሆይ ካርቱም በነበሩበት ጊዜ ደህና አድርገው ተመልክተዋል። በዚያን ጊዜ ጃንሆይ ማናቸውንም ጉዳይ በከፍተኛ ትዕግሥት ያሳለፉት፤ ጠላት ከአገራችን ከተባረረ በኋላ፤ የእንግሊዞቹ የጦር መሪዎች ተንኮልና ዕብሪት በቀላሉ ሊወገድ ይችላል በሚል ተስፋ ነበር። እነሱ ግን፤ ምንም እንኳ ፋሽስት ከአገራችን እንዲባረር (ለራሳቸው ሲሉ) አርበኞቻችንን ይዘው ከግርማዊነትዎ ጋር ሆነው የተዋጉልንና በመጨረሻም ድሉን ያስገኙልን ቢሆኑም፤ ኢትዮጵያ በሙሉ ነፃነት በንጉሠ ነገሥቷ እየተመራች መንግሥቷን እንድታቋቁም የሚፈልጉ አይደሉም። ዛሬም የምናየው ካርቱም ላይ ሲያሳዩን የነበረውን ይህንኑ የተንኮል ሐሳባቸውን ነው።

አሁን ለዚህ ችግራችን ምን ማድረግ እንደሚሻል ጃንሆይ ያዘዙትን ጥያቄ እመልሳለሁ። በእኔ በኩል የማቀርበው ሐሳብ በዲፕሎማሲ ዘዴ እንድ ሙከራ እናድርግ የሚል ነው። ይህችን የዲፕሎማሲ ዘዴ የምትባለዋን ነገር እኔና ወዳጄ የጃንሆይ አገልጋይዎች አቶ ሎሬንሶ ታዕዛዝ ሎንዶን ሆነን ብዙ ጊዜ ስንሚገትባትና ስንጣላባት፣ አልፎ አልፎም ስንስማማባት የኖረች ቃል ነች። ዛሬ ግን አጋጣሚ ሆኖ ለጃንሆይ የማቀርበው ሐሳብ የዲፕሎማሲን ዘዴ እንከተል የሚል ስለሆነ፣ ወዳጄ አቶ ሎሬንሶን እንደሚያረካው ተስፋ አደርጋለሁ።

የደቡቡን ጦር እየመራ ብዙዎቹን ግዛቶቻችንን ከፋሽስት ይዞታ ካስለቀቀ በኋላ፣ በቅድሚያ አዲስ አበባን ለመያዝ የቻለውን ጄኔራል ካኒንግሐምን ጃንሆይ በነገው ዕለት እዚሁ በገነተ ልዑል ቤተመንግሥተዎ መጥቶ ስለ መልካም አገልግሎቱ የኢትዮጵያን ከፍተኛ ኒሻን ለመሸለም የክብር ጥሪ ቢልኩለት ጥሩ ዘዴ ይመስለኛል። ካኒንግሐም ጥሪውን አክብሮ ከመጣና የኒሻን ሽልማቱን ከተቀበለ በኋላ፣ ጃንሆይ አቶ መኩንን ደስታን በአስተርጓሚነት ይዘው፣ ለኢትዮጵያ ዘመናዊ አስተዳደር አዲስ መንግሥት ለማቋቋም መወሰንዎንና ስለዚሁም ጉዳይ የጦር አዛዡ ሊያደርግ የሚችለውን እርዳታ ቢጠይቁት የሚሻል ይመስለኛል። በዚህ ሐሳብ ካኒንግሐም እተባበራለሁ ካለ፣ መግባባታችንን ልንቀጥል እንችላለን። ነገር ግን፣ ካኒንግሐም ለመተባበር የማይችል ከሆነ፣ ግርማዊነትዎ ለኢትዮጵያ ሕዝብ አስተዳደር አስፈላጊ የሆነውን አዲስ መንግሥት በ24 ሰዓቶች ውስጥ አቋቁመው መግለጫውን ለዓለም መንግሥታት ማስታወቅ የተገባ ይሆናል። በዚያን ጊዜ እነ ካኒንግሐም ሳይሆኑ፣ እነ ቸርችልና ኤደን ምን አስተያየት እንደሚሰነዝሩ እናያለን። በተጨማሪ ለማሳሰብ የምፈልገው፣ ካኒንግሐም የጃንሆይን ሐሳብ ከተቀበለ የሚሰጠው የኒሻን ሽልማት፣ የዳግማዊ ምኒልክ ታላቅ ኮርዶን ቢሆን ይሻላል። የሥላሴን ታላቅ ኮርዶን ለማቅረብ ፈልጌ ነበር። ነገር ግን ላሰው ደረጃ የሚበዛበት ይመስለኛል ... "

አቶ ሎሬንሶ ታዕዛዝ፤

" ... ወዳጄ አቶ ወልደጊዮርጊስ ያቀረባት፣ "የዲፕሎማሲ ዘዴ" በእውነቱ ዛሬ ጃንሆይ ለአጋጠማቸው ከባድ ሥራ የምትስማማ መሆኗን እኔም እምንባታለሁ። በዚህ በሠለጠነው ዓለም የሕግና የፖለቲካ ሣይንስ ትምህርት ለማግኘት የታደሉት ሰዎች፣ ብዙ ጊዜ ለሥራቸው መመርኮዣ የሚያደርጉት የዲፕሎማሲን ጥበብ ነው። በተለይ የአገር አመራርንና የውጭ ግንኙነቶችን በሚመለከት ጉዳይ፣ ከጃንሆይ አጠገብ መሥራት ይህች የዲፕሎማሲ ጥበብ የተባለችዋን ለማወቅ ዕድል ይሰጣል። አቶ ወልደጊዮርጊስም ዛሬ ይህንን ግሩም የሆነ በዲፕሎማሲ ጥበብ የተገነባ ሐሳብ ያቀረበው፣ ከጃንሆይ ጋር ለብዙ ዓመታት በቅርብ በመሥራት ያገኘው የትምህርት ውጤት ስለሆነ፣ የሚደነቅና የሚከበር ነው። ቅድም አቶ ወልደጊዮርጊስ እንደጠቀሰው፣ ሁላችንም በሎንዶን ጃንሆይን በምናገለግልበት ዘመን፣ የዲፕሎማሲን ጥበብ በመጠቀም ረገድ ብዙውን ጊዜ እንስማማም ነበር። በየጊዜው የሁለታችንንም የተለያየ ሐሳብ እያዳመጡ፣ እንደ አስተማሪና እንደ አባት እየመከሩ የሚዳኙን ጃንሆይ ነበሩ። ዛሬ ግን

አቶ ወልደጊዮርጊስ እንደሰጠው አስተያየት ከሆነ፣ ስለ አገራችን የውጭ ግንኙነቶች ጉዳይ የሁለታችንም አስተሳሰብ ወደ መቀራረቡ ጉዳና አዘንብሎ ስለተገኘ፣ ያጋለ ደስታዬን እየገለጥኩ ወደ መነሻው ጉዳያችን ተመልሼ የእኔን አስተያየት ለማቅረብ የጃንሆይን ፈቃድ እጠይቃለሁ።

አቶ ወልደጊዮርጊስ ባቀረበው ሐሳብ፣ በኒሻን ሽልማት ሰበብ ጃንሆይ ጄኔራል ካኒንግሐምን ጠርተው፣ በንጉሠ ነገሥትነታቸው ኢትዮጵያን ለመምራት አዲስ ካቢኔ የሚያቋቁሙ መሆናቸውን ቢገልጹለት በጣም ጥሩ ነው ብዬ አምናለሁ። እዚህ ላይ ካኒንግሐም የሚሰጠው መልስ <u>ሁለት ዓይነት</u> ሊሆን እንደሚችል መጠበቅ አለብን። ይኸውም፣ "እስማማለሁ"፣ ወይም "አልስማማም"፣ ነው። **አልስማማም የሚል ከሆነ፣ የማይስማማው በማን ስም እንደሆነ መጠየቅ ይኖርብናል። <u>የማይስማማው በጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል ስም ሆኖ ነው ካለ፣</u> በአዲስ አበባ የሚገኘው ንፋስ ስልክ የተባለው የኢንተርናሽናል መገናኛችን በእንግሊዞች እጅ ስለተያዘብን ይለቀቅልንና፣ ንጉሠ ነገሥታችን ከጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል ጋር መልዕክት መለዋወጥ ያስፈልጋቸዋል ብለን እንጠይቃለን። ነገር ግን የማይስማማው በራሱ ሐሳብ ብቻ ከሆነ፣ የኢትዮጵያ ጉዳይ በእሱ ሐሳብ መወሰን ስለሌለበት፣ ጃንሆይ አዲሱን ካቢኔ አቋቁመው አገሪቱን ለመምራት እርምጃ መውሰድ ይገባቸዋል እላለሁ ... "**

ራስ ካሣ፣

" ... አሁን ወልደጊዮርጊስና ሎሬንሶ በየተራ የተናገራችሁትን እንደአዳመጥኩት፣ ሁለታችሁም የተለያየ ሐሳብ አላቀረባችሁም። አነጋገራችሁ ካልሆነ በቀር፣ የሐሳባችሁ መሠረት አንድ ዓይነት ነው። እርግጥ እዚያ ሎንዶን አብራችሁ ጃንሆይን ስታገለግሉ፣ በመካከላችሁ ይገጥማችሁ በነበረው የሥራም የሐሳብም አለመስማማት ስትፋታተጉ መኖራችሁን ጠቅሳችኋል። እንዲያውም በምትተዋወቁበት መንገድ ደህና አድርጋችሁ ተነጋግራችኋል ማለትም ይቻላል። ይኸ መቸም የናንተው የራሳችሁ የግላችሁ ጉዳይ ነው። ከእንግዲህም ልጅነት ስለሚያበቃ፣ ለመጣጣምና ለመስማማት ገላጋዩን መድኃኒት ፈልጉ ለማግኘት ብርቱ ጥረት ማድረግ ይኖርባችኋል።

... አቶ ሎሬንሶ፣ አቶ ወልደጊዮርጊስ ያቀረበውን ሐሳብ መደገፉን ከተናገረ በኋላ፣ ጃንሆይ አዲስ መንግሥት ለመሾም ማሰባቸውን ለእንግሊዙ የጦር አዛዥ ሲያማክሩት፣ <u>አልስማማም ያለ እንደሆነ፣ በማን ስም ሆኖ እንደሚናገር መጠየቅ አለብን</u> ብሏል። እዚህ ላይ ለእኔ እንደታየኝ አንድ ልክ ያልሆነ ነገር አለ። መጀመሪያውኑ ጃንሆይ ከቤተመንግሥታቸው ጠርተው የሚሸልሙትና ጉዳያቸውን የሚያማክሩት ሰው፣ የእንግሊዝ ንጉሥና መንግሥት እንደራሴ ነው ብለው ነው? ወይስ የጦር አዛዥ ሆኖ አዲስ አበባን በመያዙ ብቻ ነው? ... <u>መጀመሪያ ይህንን መለየት ያስፈልጋል።</u> ሁለተኛ፣ ይኸ የጦር አዛዥ የጃንሆይን ሐሳብ አዳምጦ እስማማለሁ ካለ፣ በክብር አስተናግዶ ለመሸኘት፣ አልስማማም የሚል ከሆነ ደግሞ አንተን አናዳምጥም ብሎ

የታሰበውን መፈጸም ያስፈልጋል፣ ሲል ሎሬንሶ ያቀረበውን ሐሳብ ለመቀበል እቸገራለሁ። ስለዚህ መጀመሪያ እንዳልኩት፣ ይኸ የጦር አለቃ የሚሠራውም ሆነ የሚናገረው፣ በእንግሊዝ ንጉሥና መንግሥት ስም መሆኑ ካልተረጋገጠ፣ ጃንሆይ መሸለምም፣ ከዚያም አልፎ ስለ መንግሥታቸው ጉዳይ ማማከርም የለባቸውም እላለሁ ... "

**ጃንሆይ፣**

" ... አሁን ራስ ካሣ ያነሣኸው ጥያቄ ትክክለኛውን ስለሆነ፣ ጉዳዩ በግልጽ መታወቅ አለበት። ስለዚህም እኔው ራሴ መልሱን ልሰጥህ እፈልጋለሁ።

... አሁን ባለንበት ሰዓት ከእንግሊዝ መንግሥት በኩል ከጄኔራል ካኒንግሐም በስተቀር ሌላ ተጠሪ የሆነ ከፍተኛ ሰው የለም። ስለዚህ፣ ለጊዜው የመንግሥቱ ወኪል አድርገን ጉዳያችንን ማነጋገር ያለብን እሱን ነው። እርግጥ! ወዳጃችን ብሪጋድየር ጄኔራል ሳንድፎርድ በምሥጢር የነገሩን አንድ ነገር አለ። ጄኔራል ካኒንግሐም አዲስ አበባ አይቆይም። በጥቂት ቀናት ውስጥ የእንግሊዝ ቅኝ ግዛት የዑጋንዳ አገረ ገዥ ሜጀር ጄኔራል ፊልፕስ ሚቼል የተባለ ሰው፣ ለኢትዮጵያ ጉዳይ የፖለቲካ ኃላፊ ሆኖ አዲስ አበባ ይመጣል ተብሎ ይጠበቃል። ለዚሁ ለጄኔራል ሚቼል ምክትል ሆኖ እንዲሠራ የተመደበውም፣ ቀደም ሲል የካኒንግሐም ረዳት ሆኖ ሲሠራ የቆየው ብሪጋድየር ጄኔራል ሞሪስ ለሽ (Maurice Luch) የተባለ የጦር መኰንን ነው። ይኸ ብሪጋድየር ለሽ የተባለው ሰው ከዚህ ቀደም የመጀመሪያው የዓለም ጦርነት ከተፈጸመ በኋላ ለሦስት ዓመታት አዲስ አበባ በእንግሊዝ ሌጋሲዮን በመሥራት አገራችንን የሚያውቅ ነው። ከወዳጃችን ከብሪጋድየር ጄኔራል ሳንድፎርድ ጋር የጋብቻ ዝምድና አላቸው። ይኸውም ሁለቱም ባለቤቶቻቸው እህትማማች በመሆናቸው ነው። ...

ይሁን እንጂ፣ እነዚህ ባለሥልጣኖች ከመንግሥታቸው የተሰጣቸው ኃላፊነት እስከምን ድረስ እንደሆነ፣ ለጊዜው የምናውቀው ነገር ስለሌለ፣ ጊዜ ሳናባክን በቶሎ የመንግሥታችንን ሥራ ብንጀምር ይሻላል በማለት ነው፣ ጄኔራል ካኒንግሐም ከአዲስ አበባ ሳይሄድ ማነጋገር የፈለግነው። ... እንግዲህ! ራስ ካሣ ለጠየቅከው፣ ጄኔራል ካኒንግሐምን የምናነጋግረው ለጊዜው አዲስ አበባ የሚገኘው የእንግሊዝ መንግሥት ተጠሪ እሱ ብቻ መሆኑን ተረድተን ነው። ስለዚህ ወልደጊዮርጊስ እንዳቀረበው ሐሳብ፣ የዳግማዊ ምኒልክን ታላቅ ኮርዶን ኒሻን ከሸለምነው በኋላ፣ አዳዲስ ሚኒስትሮች በመሾም ሥራችንን ለመጀመር ማሰባችንን እንገልጽለታለን እንጂ፣ ያንተ ሐሳብ ምንድን ነው? ብለን ምክር አንጠይቀውም። ይህንን ስንነግረው ለመስማማት መንግሥቴን መጠየቅ አለብኝ ቢል፣ ማለፊያ ነው። እኛም ጠይቀህ በቶሎ አስታውቀን እንለዋለን። ነገር ግን የማልስማማው በራሴ ሥልጣን ነው ካለ ደግሞ፣ እኛ ውዝግብ ውስጥ ሳንገባ ሎሬንሶ እንደተናገረው፣ ያሰብነውን እንፈጽማለን እንጂ ወደ ኋላ አንልም ... "



ጄኔራል ካኒንግሐም፣ በኬንያ የሚገኘው የታላቋ ብሪታንያ ጦር አዛዥ

ራስ አበበ አረጋይ፤

" ... ጃንሆይ የተናገሩት ሁሉ በጣም ግልጽ ስለሆነ፤ ዛሬ ያለንበትን ሁኔታ ለመረዳት ከዚህ የበለጠ ማብራሪያ አያስፈልገንም። ጃንሆይ ነፃነታችንን ይዘው በአገርዎ በኢትዮጵያና በሕዝብዎ መካከል ከተገኙልን በኋላ፤ ጊዜ ሳይባክን በቶሎ አገረ ገዥዎችንና ሚኒስትሮችን በመሾም አዲሱን አስተዳደር ለመጀመር ያሰቡት በጣም አስፈላጊና ጊዜ መፍጀት የሌለበት ጉዳይ ነው። ሕዝብዎም ይህንን ለመስማት አሰፍስፎ እንደሚጠብቅ የታወቀ ነው። እዚህ ላይ! እኔን አንድ የሚያሳስበኝ ነገር ስለአለ፤ ግርማዊነትዎ ለመናገር እንዲፈቅድልኝ እለምናለሁ።

... ከእነዚህ ካለፉት ሦስት ቀናት ጀምሮ የምናየው የእንግሊዞች ሁኔታ፤ የሚያሳስበን እንጂ የሚያዝናናን አይደለም። የአገራችንን አስተዳደር በሙሉ ይዘውታል። በዘመናዊ መሣሪያዎች የታጠቀ የጦር ኃይል አቁመዋል። በወታደሮቹም ውስጥ ከእኛ ከኢትዮጵያ በኩል አንድም ሰው አልመደቡም። ሁሉም የእንግሊዞቹን ቋንቋ የሚናገሩ፤ ከቅኝ ግዛቶቻቸው ከጥቁሮቹ አገሮች አስታጥቀው ያመጧቸው ናቸው። ይህን ሁሉ ስንመለከት ለአገራችን አስተዳደር የያዙትን ሥልጣን በወግ አስረክበው በቶሎ ለመልቀቅ የሚያስቡ አይመስልም። እኔ ይህን ስናገር፤ ጃንሆይ እርምጃ ለመውሰድ ያቀዱት ሐሳብ እንዲዘገይ ወይም እንዲለወጥ ለማሳሰብ አይደለም። ጃንሆይ የመንግሥትዎን ሚኒስትሮች መርጠው ለመሾምና በየሥራው ዘርፍ ለመመደብ መወሰንዎን እንግሊዞቹ ሲያውቁ፤ ምናልባት <u>እንስማማም</u> የሚል መልስ የሰጡ እንደሆነ፤ ግርማዊነትዎ ያሰቡትን ይፈጽማሉ እንጂ፤ ወደኋላ አይሉም የተባለውን በጥንቃቄ አድምጫለሁ። እንደእኔ ... እንደእኔ ... እዚህ ላይ ደህና አድርገን ጉዳዩንና የሚያስከትለውን ችግር ማጥናት ይኖርብናል። ጃንሆይ የሾሟቸው ሚኒስትሮችም ሆኑ አገረ ገዥዎች እንግሊዞቹ እስካሁን የያዙትን ሥራውንና ሥልጣኑን ለእያንዳንዳቸው በሰላም ካላስረከቧቸው፤ <u>እነዚህ ሰዎች በመሾማቸው ብቻ ምን መሥራት ይችላሉ?</u> ... በእኔ አስተያየት ይኸ ችግር ከደረሰብን ወዲያውኑ አጸፋውን ለመመለስ አንድ ዓይነት ዝግጅት አድርገን ብንጠብቅ ይሻላል። ጃንሆይ እንደሚያውቁት፤ አርበኞችም ትጥቃቸውን አልፈቱም። አስፈላጊ በሆነበት ቦታ ሁሉ ትዕዛዝዎን ለመፈጸም የሚጠባበቁ ናቸው ... "

ጃንሆይ፤

" ... አበበ አረጋይ በእኛና እዚህ አዲስ አበባ ባሉት የእንግሊዝ የጦር አለቆች መካከል ሊደርስብን የሚችለው ችግር የት ላይ እንደሆነ ደህና አድርገህ ተገንዝበኸዋል። ይህን ስብሰባ እንደከፈትን ወልደጊዮርጊስ በደህና ሁኔታ አስረድቷል። እነዚህ የእንግሊዝ ልዩ ልዩ የጦር አዛዦች፤ የወዳጃችን የሚስተር ቸርችልን መምሪያ በራሳቸው ፍላጐት እየጣሱ፤ በእኛና በኢትዮጵያ ነፃነት ጉዳይ ይፈጽሙብን የነበረውን ተንኮል ካርቱም በነበርንበት ጊዜ እናስታውሳለን። ዛሬም አዲስ አበባ

ከገባን በኋላ እንደምናየው፣ አስተያየታቸው አልተሻሻለም። ስለዚህ፣ ከዛሬ ጀምሮ በማናቸውም መልክ በሚደርስብን ሁሉ ቀራጥ ሆነን መገኘት አለብን። የሚመጣብንን በመጣበት አኳኋን ለመመከት ደካማነት አናሳይም። ሕይወታችን አለ ድረስ፣ በምንም መንገድ የኢትዮጵያ ነፃነት ከአንዱ ኮሎኒያሊስት ወደ ሌላው እንደ ዕቃ አይተላለፍም። ከእንግዲህም ወዲህ መንግሥታችንን አቋቁመን አገራችንን በነፃነት መምራት እስከምንችል ድረስ፣ አበበ አረጋይ እንዳልከው የአርበኞቻችን ብቻ ሳይሆን፣ የእኛም ትጥቅ ሳይፈታ በተጠንቀቅ መቆየት አለበት።

አሁን በእኛ በኩል የተወሰነውን እናስታውቃችኋለን።

1ኛ/ ነገ ጠዋት ግንቦት 1 ቀን 1933 ዓ.ም ጌታሁን ተሰማና መኰንን ደስታ ጄኔራል ካኒንግሐም ቢሮ ሄዳችሁ፣ ስለ አገልግሎቱ ያዘጋጀንለትን ኒሻን ከቤተመንግሥታችን መጥቶ እንዲቀበል ጥሪያችንን አቅርቡለት!

2ኛ/ ጄኔራል ካኒንግሐም የሚሰጠው መልስ ቀና ሆኖ መነጋገር ብንችልም ባንችልም፣ ለመንግሥታችን አስተዳደር የሚያስፈልገውን ለመፈጸም ቆርጠናል። ... ሁላችሁም በየበኩላችሁ የምታስቡትን በግልጽና እውነትን በያዘ መንገድ ስለአቀረባችሁልን ማለፊያ ሠርታችኋል ... "

ከዚህ በላይ እንደተገለጸው፣ ንጉሠ ነገሥቱ በገነተ ልዑል ቤተመንግሥታቸው ባደረጉት ጉባኤ ላይ በተወሰነው መሠረት፣ ጄኔራል ካኒንግሐም ዘንድ የተላኩት አቶ መኰንን ደስታና አቶ ጌታሁን ተሰማ የሚከተለው መልስ ተሰጣቸው።

1ኛ. ኒሻኑን ለመቀበል ጄኔራል ካኒንግሐም በመጀመሪያ ካይሮ ያሉትን አለቆቹን አማክሮ ማስፈቀድ ስለአለበት፣ መልሱን በቶሎ መስጠት ይቸገራል።

2ኛ. ጄኔራሉ ለልዩ መልዕክት በአስቸኳይ ወደ ደቡብ አፍሪካ እንዲሄድ ስለታዘዘ፣ ከንጉሠ ነገሥቱ ጋር ተገናኝቶ ለመነጋገር ጊዜ ያጥረዋል።

3ኛ. የውጋንዳ አገረ ገዥ ጄኔራል ፊሊፕ ሚቼል የምሥራቅ አፍሪካ ጦር የፖለቲካ ሹም በሁለትና ሦስት ቀናት ውስጥ አዲስ አበባ ስለሚመጣ፣ ንጉሠ ነገሥቱ ከእሱ ጋር መነጋገር ይችላሉ።

ጃንሆይ ይህ መልስ ሲደርሳቸው፣ በጉባኤው ላይ በተወሰነው መሠረት አዲስ ካቢኔ ለማቋቋም እርምጃ ወሰዱ። *

* የጽሕፈት ሚኒስቴር ቃለ ጉባኤ ሚያዝያ 30 ቀን 1933 ዓ.ም

# ምዕራፍ ፲

## ጃንሆይ ሚኒስትሮቻቸውን ሾሙ፤ እንግሊዞች በብርቱ ተቃወሙ*

እ.ኢ.ት.አቆ ቅዳሜ ግንቦት 2 ቀን 1933 ዓ.ም ከእኩለ ቀን በፊት በአምስት ሰዓት፤ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ከዚህ ቀጥሎ የተዘረዘሩትን ሚኒስትሮች ሾመው፤ መንግሥታቸውን ለመምራት መወሰናቸውን በአዋጅ አስታወቁ።

1. ደጃዝማች መኰንን እንዳልካቸው፤ — የአገር ግዛት ሚኒስትር፤
2. አቶ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፤ — ጸሐፊ ትዕዛዝ ተብለው ታላቁን ማሕተም ጠባቂና የጽሕፈት ሚኒስትር፤
3. አቶ ሎሬንሶ ታዕዛዝ፤ — ብላቴን ጌታ ተብለው፤ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር
4. አቶ መኰንን ደስታ (ኋላ ደጃዝማች) — የትምህርትና የሥነ ጥበብ ሚኒስትር፤
5. አቶ ገብረእግዚአብሔር ደስታ — ነጋድራስ ተብለው የንግድና የኢንዱስትሪ ሚኒስትር፤
6. ብላታ አየለ ገብሬ፤ — የፍርድ ሚኒስትር፤
7. አቶ በላቸው ያደቴ (ኋላ ብላቴን ጌታ) — የፖስታ፣ የቴሌግራፍና የቴሌፎን ሚኒስትር፤

የእነዚህ ሰዎች ሹመት በይፋ እንደተገለጸ፤ የኢትዮጵያን አስተዳደር ሥልጣን ይዘው የሚመሩት የእንግሊዝ የጦር ሹማምንቶች፤ ንጉሠ ነገሥቱ ሳያማክሩን ወይም ቀደም ብለው ሳይነግሩን በወሰዱት እርምጃ አንስማማም በማለት ብርቱ ተቃውሞ አደረጉ። የእንግሊዝ ወታደራዊ አስተዳደር የፖለቲካ ምክትል ሹም የተባለው ብሪጋድየር ዤኔራል ሞሪስ ለሽ፤ የሚኒስትሮቹን ሹመት የሰማው ለሥራ ጉዳይ ወደ ወሎ ክፍለ ሀገር በሚጓዝበት ጊዜ ስለነበረ፤ ጉዞውን አቋርጦ ከፍ ባለ ብስጭት እየገሠገሠ ወደ አዲስ አበባ ተመለሰ። ወዲያውም፤ ወደ ገነተ ልዑል ቤተመንግሥት ሔዶ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን በፍጥነት ማነጋገር አለብኝ አለ። ከጥቂት ቀናት በፊት የንጉሠ ነገሥቱ ዋና የእልፍኝ አስከልካይ ሆነው የተሾሙት ወጣቱ ሻለቃ ዓቢይ አበበ (ኋላ ሌፍትናንት ዤኔራል) የመጣኸው ያለ ቀጠሮ ስለሆነ፤ ጃንሆይ እስኪዘጋጁ ጥቂት ጊዜ መጠበቅ አለብህ አሉት። ብሪጋድየር ለሽ የበለጠ ተናደደ። እኔ በታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ስም የኢትዮጵያ አስተዳደር ኃላፊ ነኝ። ንጉሠ ነገሥቱን ለማነጋገር ደጅ መጥናት የለብኝም አለ። ዋናው

---

* የጊታሁን ተሰማ ማስታወሻ

## ሰባቱ የመጀመሪያዎቹ የቀ.ኃ.ሥ የካቢኔ ሚኒስትሮች



ደጃዝማች መኰንን እንዳልካቸው
የአገር ግዛት ሚኒስትር።



አቶ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ
ጸሐፊ ትዕዛዝ ተብለው
የጽሕፈት ሚኒስትር።



አቶ ሎሬንሶ ታዕዛዝ
ብላቴን ጌታ ተብለው
የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር።



አቶ መኰንን ደስታ
የትምህርት ሚኒስትር።



ነጋድራስ ገብረእግዚአብሔር ደስታ
የንግድ ሚኒስትር።



ብላታ አየለ ገብሬ
የፍርድ ሚኒስትር።



አቶ በላቸው ያደቴ ብላቴን ጌታ
ተብለው የፖስታ ቴ.ቴ ሚኒስትር።

እልፍኝ አስከልካይ አልተበገሩለትም። ያለ ቀጠሮ በመምጣትህ፣ ትንሽ መጠበቅ አለብህ ብለው የእንግዶች ማረፊያ የሆነውን ሳሎን አስከፈቱለት። ጃንሆይ ሚኒስትሮቹን በመሾም በወሰዱት እርምጃ፣ እንግሊዞቹ ምን ያህል ብስጭት እንደአደረባቸው በቅድሚያ ዜናውን በመስማታቸው፣ ብሪጋድየር ለሽ ከመምጣቱ በፊት ዋና ዋና ረዳቶቻቸውን ይዘው ለመልሱ ተዘጋጅተውበት ነበር።

በጃንሆይ ቢሮ ልዑል ራስ ካሣ፣ ክቡር ራስ አበበ አረጋይ፣ ከአዲሶቹ ሚኒስትሮች መካከል፣ የአገር ግዛት ሚኒስትሩ ደጃዝማች መኰንን እንዳልካቸው (ኋላ ቢትወደድ)፣ የጽሕፈት ሚኒስትሩ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፣ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ብላቴን ጌታ ሎሬንሶ፣ የትምህርት ሚኒስትሩ አቶ መኰንን ደስታ፣ የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር አቶ ጌታሁን ተሰማ፣ የግርማዊነታቸው ልዩ ጸሐፊ አቶ ተፈራወርቅ ኪዳነወልድ ተገኝተው ነበር። ብሪጋድየር ጄኔራል ለሽ ጃንሆይ ቢሮ ገብቶ ለንጉሠ ነገሥቱ ወታደራዊ ሰላምታ ካቀረበ በኋላ፣ ወንበር ሲሰጠው የሚከተለውን ተናገረ።

**ጃንሆይ፣**

> ዛሬ ከአዲስ አበባ ውጭ የጀመርኩትን የሥራ ጉብኝት አቋርጬ በአስቸኳይ እርስዎን ለማነጋገር የመጣሁት፣ ግርማዊነትዎ ግብዎ ምን እንደሆነ ሳያማክሩንና ሳንስማማበት ሚኒስትሮች ሾሚያለሁ ብለው አዋጅ በማስነገርዎ፣ የኢትዮጵያን አስተዳደር በሚመሩት በታላቋ ብሪታንያ የጦር ኃይል አዛዦች ስም ሆኜ ከፍተኛ ቅሬታችንን እየገለጥኩ፣ የተደረጉትን ሹመቶች የማንቀበል መሆናችንን ለማስታወቅ ነው። በተለይ ግርማዊነትዎና አማካሪዎችዎ እንዲያውቁት የሚያስፈልገው፣ ኢትዮጵያ ከጠላት እጅ በሙሉ ተላቅቃ ገና ነፃነቷን ያላገኘች መሆንዋን ነው። ዛሬ ባለንበት በዚህ በግንቦት ወር (1941 ዓ.ም) ሁለተኛው ሳምንት ላይ ያለውን ሁኔታ ከተመለከትነው፣ በሰሜን በኩል አምባላጌ ላይ የመሸገው የዱካ ዳ አስታ ጦር ድል ለመሆን ከመቃረቡ በስተቀር፣ ሌሎቹ በጉንደር የሰፈረው የጄኔራል ናዚ እና በጅማ ያለው የጄኔራል ጋዚራ ጦሮች ገና አልተደመሰሱም። ስለዚህ፣ ከፊታችን የተደቀኑት ፕሮብሌሞች እስከሚወገዱ ድረስ፣ የታላቋ ብሪታንያ የጦር ኃይሎች ያለባቸው ኃላፊነት እጅግ የከበደ ነው። ... ስለ ኢትዮጵያ ጉዳይ በቅርቡ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት የጦር ካቢኔ ያደረገውን ውሳኔ፣ ለግርማዊነትዎ ማስታወስ እፈልጋለሁ። ኢትዮጵያ የዛሬው ጠላታችን የፋሺስት መንግሥት ቅኝ ግዛት በመሆኗ፣ ታላቋ ብሪታንያ ድል እያደረገች ከያዘቻቸው ከጣልያን ኮሎኒዎች ከነ ሊቢያ፣ ኤርትራና ሱማሌ ጋር በእንግሊዝ ወታደራዊ አስተዳደር ሥር እንድትቆይና፣ ከጦርነቱ ፍጻሜ በኋላ በሚደረገው የሰላም ጉባኤ የወደፊት ዕድሏ እንዲታይ ተወስኗል። ስለዚህ፣ ኢትዮጵያ አሁን የምትገኘው በታላቋ ብሪታንያ ወታደራዊ አስተዳደር ውስጥ ስለሆነ፣ እኔ ብሪጋድየር ጄኔራል ሞሪስ ለሽ፣ የምሥራቅ አፍሪካ ጦር ለኢትዮጵያ ጉዳይ ምክትል የፖለቲካ ሹም ስለሆንኩ፣ የኢትዮጵያን አስተዳደር በሙሉ ሥልጣን የምመራ እኔ መሆኔ እንዲታወቅልኝ እፈልጋለሁ። በተጨማሪ፣ በታላቋ ብሪታንያ የጦር ካቢኔ ስብሰባ ላይ ንግግር ተደርጐ ውሳኔ ከተሰጠባቸው ጉዳዮች መካከል፣ አንዳንዶቹን ግርማዊነትዎን የሚመለከቱትን ልጠቅስልዎ እወዳለሁ።

1. የእንግሊዝ ወታደራዊ አስተዳደር ለኢትዮጵያና ለሕዝቦቿ ጠቃሚነታቸው ታውቆ የሚያዘጋጃቸው አዋጆች ሁሉ፣ ለሕዝቡ የሚገለጹት በግርማዊነትዎ ስም እንዲሆን ተፈቅዷል።

2. ከኢትዮጵያ ግዛቶች ውስጥ ለታላቋ ብሪታንያ ጦር ኃይሎች አስፈላጊ ያልሆኑት አውራጃዎች እየተለዩ፣ በቀጥታ በግርማዊነትዎ መሪነት እንዲተዳደሩ ይደረጋል።

3. ወደፊት በግርማዊነትዎና በእንግሊዝ መንግሥት መካከል የሚኖረው ግንኙነት፣ በፖለቲካው ሹም አማካይነት እንዲከናወን ተወስኗል።

የእንግሊዝ የጦርና የቅኝ ግዛት ጉዳይ ሚኒስትሮች፣ ከጦር አዛዦቹ ጋር በመተባበር በኢትዮጵያ ላይ የወሰዱት አቋም ምን እንደሆነ፣ ከዚህ በላይ እንደተገለጸው ብሪጋድየር ጄኔራል ሞሪስ ለሽ የተናገረውን፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በታላቅ ትዕግሥትና እጅግ በረጋ መንፈስ ካዳመጡ በኋላ፣ በታወቁት የሐርቨርድ ዩኒቨርሲቲ ምሩቅ በአቶ መኰንን ደስታ አስተርጓሚነት የሚከተለውን መልስ ሰጡ።

አሁን እርስዎ የተናገሩትን ሁሉ በትክክል አድምጫለሁ። በመጀመሪያ የምሰጠው መልስ፣ በኢትዮጵያ ጉዳይ የእንግሊዝ መንግሥት የጦር ካቢኔ ያደረገው ውሳኔ ነው ብለው ዘርዝረው የተናገሩትን፣ እኔ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ንጉሠ ነገሥት የምሰማው ለመጀመሪያ ጊዜ ነው። ከዚህም በላይ ወዳጃችን ነው ብለን ከልባችን የምናምነውና ባለውለታችን ነው የምንለው የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ይህንን የመሰለ የኮሎኒያሊስት አስተዳደር ቀንበር እንደሚጭንብን ጨርሶ ያላሰብነውና ጨርሶ ያልጠበቅነው መሆኑን በቅድሚያ እንዲገነዘቡት እፈልጋለሁ።

እርስዎ ንግግርዎን የጀመሩት ሳንመካከርበትና ሳንስማማበት ሚኒስትሮች በመሾማቸው መንግሥትዎ ቅር መሰኘቱንና ሹመቱንም አለመቀበሉን ነው። ይኸንን እኛ ትልቅ ቁም ነገር አድርገን አንቆጥረውም። ስለሚኒስትሮቹ ሹመት ወደፊት ተነጋግረንበት ለመስማማትም ላለመስማማትም እንችላለን። ከዚህ ይልቅ እርስዎ የተናገሩት ትልቁ ጉዳይ፣ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ኢትዮጵያን የምትቆጥራት እንደ ሊቢያና ሱማሌ የጣልያን ቅኝ ግዛት አድርጋ ስለሆነ፣ የምትተዳደረው በእንግሊዝ ጦር ሠራዊት ሥር ነው ሲሉ የሰጡት መግለጫ ነው። ይህ ስለ ኢትዮጵያ ጉዳይ የእንግሊዝ የጦር ካቢኔ መክሮ ያደረገው ውሳኔ ነው ብለው እርስዎ ዛሬ የሰጡን መግለጫ፣ እኔን ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥትና አሥራ አራት ሚሊዮን የሚገመተውን መላውን ሕዝቤን እጅግ የሚያሳዝንና እጅግ የሚያበሳጭ ከመሆኑም በላይ፣ በምንም ረገድ፣ በምንም መንገድ፣ ይህንን ውሳኔ የማንቀበለው መሆኑን እንዲያውቁት እፈልጋለሁ።

የኢትዮጵያ ሕዝብ አምስቱን ዓመታት ሳያቋርጥ በየጫካው እየተዘዋወረ በየበረሃው እየተንገላታ፣ ከወራሪው ፋሽስት ጋር ለነፃነቱ ሲዋጋና ሲሞት የቆየው፣ በመጨረሻው ከጣልያን ኮሎኒነት ወደ እንግሊዝ ቅኝ ግዛት አስተዳደር ለመለወጥ አይደለም። እርስዎ ቅድም እንደተናገሩት ከኢትዮጵያ ግዛት ውስጥ ምንም እንኳ በአንዳንድ ጥቂት ቦታዎች ላይ የፋሽስት ጦር ድል ሆኖ ጦርነቱ ባያልቅም፣ ከሰማንያ በመቶ በላይ የሆነው ግዛታችን ፋሽስት ተባርሮ ነፃነቱን አግኝቷል። ለዚህም ነፃነት ከወዳጃችን ከታላቋ ብሪታንያ ጦር ጋር አብሮ ተሰልፎ የተዋጋውና

ብዙ ጀብዱ በማሳየት መሥዋዕትነትን የተቀበለው የአገሬ የኢትዮጵያ ሕዝብ መሆኑን መዘንጋት አያስፈልግም። ይህ ሕዝብ በእኔ በንጉሠ ነገሥቱ የሚመራና ለአገሩ ነፃነት እስከ መጨረሻው ድረስ ትጥቁን የማይፈታ ስለሆነ፤ ኢትዮጵያ አሁንም የምትቀጠረው የፋሽስት ጣልያን ኰሎኒ ሆና ነው የሚባለውን ነገር ባይሰማው ይሻላል። ስለዚህ፤ የጦር ካቢኔው በኢትዮጵያ ላይ ወስኗል የሚባለውን ይህንን እጅግ አሳዛኝ አስተያየትና ፍርድ ወደ ኢትዮጵያ ሕዝብ ጆሮ እንዳይደርስ ከፍ ያለ ጥንቃቄ ማድረግ ይበጃችኋል ብለን፤ የወዳጅነታችንን አስተያየትና ምክር እንሰጣችኋለን። እኔ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥትና የምመራው ሕዝቤ፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ከፋሽስት ቀንበር ተላቀን ነፃነታችንን እንድናገኝ ምን ያህል እንደደከመልንና ምን ያህል እንደረዳን ደህና አድርገን እናውቃለን። ነፃነታችንን ስለማግኘትና ስለወደፊቱም የመንግሥት አስተዳደራችን የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት እ.ኤ.አ በየካቲት 4 ቀን 1941 ዓ.ም በፓርለማ ቀርቦ ለእንግሊዝ ሕዝብ እንደራሴዎች የሰጠውን መግለጫ ትናንት እንደተቀበልነው፤ ዛሬም ሆነ ነገ መሠረታችን እሱ ነው ብለን የምናምንበት ነው። ይህም የመንግሥት መግለጫ፤

1ኛ/ ኢትዮጵያ ነፃነቷ ተመልሶላት መንግሥቷን እንድታቋቁም ታላቋ ብሪታንያ ትደግፋለች።

2ኛ/ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት መሆናቸውንና ወደ ዙፋናቸው የመመለሳቸውን ጥያቄ ታላቋ ብሪታንያ ትስማማለች።

3ኛ/ ታላቋ ብሪታንያ በኢትዮጵያ ላይ የግዛት ይገባኛል ጥያቄ የላትም።

4ኛ/ በኢትዮጵያ ልዩ ልዩ ክፍለ ሀገሮች ውስጥ ከጠላት ጋር ለሚደረጉት ጦርነቶች የመምሪያ አሰጣጡና ቁጥጥሩ የሚካሄደው፤ ለጊዜው በታላቋ ብሪታንያ የጦር ኃይሎች ይሆናል። ይህም ቢሆን ከንጉሠ ነገሥቱ ጋር በመመካከር እንዲከናወን ይታሰብበታል።

5ኛ/ ንጉሠ ነገሡቱ ወደፊት ለአገራቸው አመራር የሚያስፈልጋቸውን ድጋፍ ሲጠይቁ በአግባቡ እየታየ የሚቻለው ሁሉ ይፈጸምላቸዋል። ...

የሚል ነው።

በኢትዮጵያ በኩል እኛ እስካሁን የምናውቀውና ተቀብለን የምንከተለው፤ ይህንን ከታላቋ ብሪታንያ መንግሥት በፓርለማ ለሕዝብ እንደራሴዎች የተገለጸውንና የሌላውም ዓለም መንግሥት የሚያውቀውን ነው።

በእኛ በኩል ከልባችን የምናስበውን ልንገልጽልዎ የምንፈልገው፤ ወዳጃችን የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ተዋጊ አርበኞቻችንን አስተባብሮ ፋሽስትን የወጋልን፤ በግፍ የተገፈፈውን ነፃነታችንን ለማስመለስ እንጂ፤ ፋሽስት ሲባረር አገራችንን በቅኝ ግዛት መልክ ይዞ ለማስተዳደር ነው ብለን የማናምን መሆናችንን ነው። አንድ ወዳጅ ወዳጁ ከደረሰበት የጠላት ጥቃት ለማዳን መጥቶ አስፈላጊውን እርዳታ ከሰጠ በኋላ፤ በወዳጁ ቤት ባለቤቱ እኔ ነኝ ብሎ መከዳውን ሲዘረጋ፤ ታይቶም ተሰምቶም የሚታወቅ ታሪክ አይደለም። ስለዚህም፤ አሁን እርስዎ እንደነገሩን <u>የጦር ካቢኔው የወሰነው፤</u> ከፋሽስት የተላቀቀችዋን ኢትዮጵያን እንደ ጣልያን ኰሎኒ ቆጥሮ፤



አቶ ጌታሁን ተሰማ

ከነፃነት በኋላ መንግሥት ሲቋቋም የመጀመሪያው የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ሆነው ተሾሙ። በጠላት ዘመን ለአምስት ዓመታት ሙሉ አርበኛ የነበሩ ናቸው። ለኢትዮጵያ ነፃነት የዘመቻ ዝግጅት ሲደረግ፤ ከነ ጄኔራል ሳንድፎርድ ጋር የሚሲዮን ቁጥር "101" አባል ሆነው ከሠሩ በኋላ፤ ጃንሆይ ደብረማርቆስ ሲገቡ በላይ ዘለቀንና ጦሩን ንጉሠ ነገሥቱ መልካም ፈቃዳቸው ሆኖ እንዲቀበሉ አስፈላጊውን አዘጋጅተዋል፤

በእንግሊዝ ወታደራዊ አስተዳደር ተይዛ እንድትቆይ ከሆነ፣ ቀደም ብዬ የገለጽኩልዎትን አሁንም እደግምልዎታለሁ። በምንም መንገድ፣ በምንም ረገድ፣ በምንም ተአምር ይህንን ውሳኔ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥትና የኢትዮጵያ ሕዝብ አይቀበሉትም። እኛ ኢትዮጵያውያን ረዥሙ የብዙው ሺህ ዓመታት ታሪካችን እንደሚመሰክረው፣ ለነፃነታችን ስንዋጋና ስንሠዋ የኖርን ነን። ዛሬም ማንኛውንም አደጋ ለመመከትም ሆነ ለመቀበል ዝግጁ ነን። መቸውንም ቢሆን ነፃነትን አጥተን ለባርነት አስተዳደር አንሸነፍም" ... በሚል ቃል ጃንሆይ ንግግራቸውን ፈጸሙ።

የታወቀው ዕብሪተኛና ስድ የሆነው ብሪጋድየር ሞሪስ ለሽ፣ የንጉሠ ነገሥቱን የመልስ ንግግር ፊቱን አኮሳትሮ በጥንቃቄ ካዳመጠ በኋላ፣ ዝርዝር መልስ መስጠት አልፈለገም። በአጭሩ " ... በጠቅላይ ሚኒስትር ዊንስተን ቸርችል የሚመራው የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት "የጦር ካቢኔ" ያደረገውን ውሳኔ፣ ግርማዊነትዎ በምንም አኳኋን የማይቀበሉት መሆንዎን ነግረውኛል። እኔም ይህንኑ ለበላዮቼ አስታውቃለሁ። በተጨማሪም በዚህ በአለንበት በግንቦት ወር ውስጥ፣ የጠቅላላው የምሥራቅ አፍሪካ ጦር ዋና የፖለቲካ ሹም የሆኑት ሜጀር ጄኔራል ፊሊፕ ሚቼል አዲስ አበባ ስለሚመጡ፣ በዚሁ ጉዳይ ከግርማዊነትዎ ጋር በሰፊው እንደሚነጋገሩበት እገልጽልዎታለሁ። በእኔ በኩል ግን፣ የሚኒስትሮችዎን ሹመትና የካቢኔ ማቋቋም ፍላጐት የማልቀበለው መሆኔን በድጋሚ እያስታወቅኩ፣ ግርማዊትዎን እሰናበታለሁ ... " በማለት የቀዘቀዘ ሰላምታ ሰጥቶ ከጃንሆይ ቢሮ ወጣ።

በዚህ ስብሰባ ላይ የተካፈሉት የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር አቶ ጌታሁን ተሰማ እንዳጫወቱኝ፣ በእንግሊዞች ሁኔታ ጃንሆይ የደረሰው ይድረስ በማለት ቆርጠው ስለነበረ፣ ለብሪጋድየር ለሽ መልሱን የሰጡት፣ በቆረጠ መንፈስ ነበር። ያለ ጥርጥር በዚህ ምክንያት መሆን አለበት ሞሪስ ለሽ መጀመሪያ ጃንሆይ ቢሮ ሲገባ ያንን የሚያህል የጉላ የዕብሪት መንፈስ ካሳየ በኋላ፣ ተሰናብቶ ሲወጣ ንዴቱን ለመቆጣጠር አለመቻሉን ከማሳየቱ በስተቀር፣ ጠቅላላ ሁኔታው ሲታይ የፉከራ መልክ አልነበረውም።

ዕብሪተኛው የእንግሊዝ ባለሥልጣን ከጃንሆይ ቢሮ ከወጣ በኋላ፣ በተሰበሰቡት ታላላቅ ሰዎች መካከል የደረሰው ነገር ፈገግታን እንደሚቀሰቅስ አቶ ጌታሁን የሚከተለውን አጫወቱኝ።

ራስ አበበ አረጋይ ስሜታቸውን ሲገልጹ፣ " ... ጃንሆይ ለእንግሊዙ ሹም የሰጡት መልስ እጅግ የሚያኮራና የኢትዮጵያን ክብር አጉልቶ የሚያሳይ መሆኑን አዳምጬ በጣም ተደስቻለሁ። ይህ ንግግር በእንግሊዝኛ እየተተረጐመ ለሰውየው ሲነገረው፣ ልክ እንደ አማርኛው ጣዕሙና ቁም ነገሩ ተሳክቶ እንደሆነ፣ ... በጣም ጥሩ ነው ..." አሉ። በዚህ ጊዜ ትርጉሙን የሠራው መኰንን ደስታ ተነክቶ ይሆን? ብለን ሁላችንም ስንጨነቅ፣ ብላታ ሎሬንሶ ያሻሽሉ መስሎአቸው፣ " ... ክቡር ራስ! ምንም አይጠራጠሩ! በእንግሊዝኛ የተደረገው ትርጉም ከአማርኛው የበለጠ እንጂ፣ አያንስም ... " የሚል አስተያየት ሰጡ። ይኸ ደግሞ ጃንሆይን የሚነካ መሆኑ ግልጽ ሆነ። ... በዚህ ሁላችንንም ሳቅ እየኰረኰረን ከጃንሆይ ቢሮ ወጣን። ጃንሆይ አንዳች ስሜት አልገለጹም።

# ምዕራፍ ፲

## ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከፊሊፕ ሚቼል ጋር፤*

ብሪጋድየር ሞሪስ ለሽ ለጃንሆይ እንደገለጸው፤ እ.ኤ.አ ግንቦት 23 ቀን 1941 ዓ.ም የእንግሊዝ የምሥራቅ አፍሪካ ጦር የፖለቲካ ሹም የሆነው ሜጀር ጄኔራል ፊሊፕ ሚቼል (Philip Mitchell) አዲስ አበባ እንደገባ፤ ወደ ገነተ ልዑል ቤተመንግሥት ሔዶ ከንጉሠ ነገሥቱ ጋር ስለ ኢትዮጵያ አስተዳደር ጉዳይ በሰፊው ተወያየ።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ሚያዝያ 27 ቀን 1933 ዓ.ም (05/05/41) አዲስ አበባ ከገቡበት ጊዜ ጀምሮ፤ የእንግሊዝ የጦር ኃይል ሹማምንቶች የኢትዮጵያን አስተዳደር ሙሉ ሥልጣን ይዘው አገሪቷን የሚመሯት እንደ አንድ ቅኝ ግዛት አድርገው በመሆኑ፤ የተሰማቸውን ብርቱ ምሬት ለጄኔራል ሚቼል ዘርዝረው ገለጹለት።

ጃንሆይ ልዩ ጸሐፊያቸውን አቶ ተፈራወርቅ ኪዳነወልድን (ጊላ ጸሐፊ ትዕዛዝ) በአስተርጓሚነት ይዘው ለጄኔራል ፊሊፕ ሚሼል (Philip Mitchell) ያስረዱትን አቶ ጌታሁን ተሰማ የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ከያዙት ማስታወሻቸው ላይ እንደሚከተለው ነግረውኛል። " ... የእርስዎ ምክትል የፖለቲካ ሹም የሆኑት ብሪጋድየር ጄኔራል ሞሪስ ለሽ፤ ባለፉት ቅርብ ቀናት እኛ ዘንድ መጥተው የታላቂ ብሪታንያ የጦር ካቢኔ ባደረገው ውሳኔ መሠረት፤ ኢትዮጵያ በአሁኑ ሰዓት የጣልያን ቅኝ ግዛት ሆና ስለምትቆጠር፤ ከጠላት ተወስደው ከተያዙት ኮሉኒዎች ከሊቢያ፣ ከኤርትራና ከሱማሌ ጋር በእንግሊዝ ወታደራዊ አስተዳደር ሥር የምትቆይ መሆኗን ነግረውናል። ይህንን ውሳኔ ፈጽሞ የማናስበውና የማንጠብቀው በመሆኑ፤ ምን ያህል እንዳሳዘነንና ምን ያህል ሞራላችንን እንደነካው ገልጸን፤ በእኛ በኩል በማናቸውም መንገድ ይህንን ውሳኔ ለመቀበል አለመቻላችንን ለብሪጋድየር ለሽ በሚገባ አስረድተናቸዋል። ዛሬ ለእርስዎም የምንገልጸው፤ ይህንኑ የጠነከረ አቋማችንን ሲሆን፤ በተጨማሪም እንግሊዝን የሚያህል ትልቅ መንግሥት፤ የኢትዮጵያን ነፃነትና ክብር ሠርዞ በኮሉኒዎች ደረጃ ላይ ይጥላታል ብለን ማመንም መቀበልም ያቃተን መሆኑን ነው።

ከብዙ ሺህ ዘመናት ጀምሮ ነፃነቷ ተከብሮ የኖረችውንና የዓለም ነፃ መንግሥታት ማህበር አባል የሆነችውን ኢትዮጵያን፤ የፋሽስት መንግሥት በጦር ኃይል ለጥቂት ዓመታት ስለያዛት ብቻ፤ "ቅኝ ግዛት" ተብላ መጠራቷ እጅግ የሚያሳዝንና እጅግ የሚያስገርም ነው። ሙሶሊኒ ኢትዮጵያን በጦርነት መያዝ ሲያቅተው፤ በዓለም ሕግ የተከለከለውን የጋዝና የመርዝ ጢስ በአውሮፕላን በመርጨት ሕዝባችንን እያቃጠለ እንደጨረሰ፤ የታላቂ ብሪታንያ መንግሥት የሚዘነጋው አይደለም። ይህ ሁሉ አሠቃቂ አደጋ በሕዝባችን ላይ ቢደርስም፤ አርበኞቻችን በየጫካውና በየበረሃው ተሰማርተው ጠላትን አስጨንቀው

* በጃንሆይና በፊሊፕ ሚቼል መካከል ስለተደረገው ንግግር፤ የጌታሁን ተሰማ ማስታወሻ

በመያዛቸው፤ ሙሶሊኒ መላ ኢትዮጵያን በእጁ አድርጎ ለመግዛት ምን ያህል እንዳቃተው፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ደህና አድርጎ ያውቃል። አሁን በመጨረሻውም የፋሽስት ጦር ተሸንፎ ከኢትዮጵያ ግዛት የተባረረውና እኛም መናገሻ ከተማችን የገባነው፤ በታላቂ ብሪታንያ ጦር ኃይል እርዳታ መሆኑን ከልባችን ብናምንበትም፤ የኢትዮጵያ አርበኞች ከእንግሊዞች ጐን ሆነው ያደረጉት ትብብርና ተጋድሎ በቀላሉ የሚገመት አለመሆኑ መታወቅ አለበት።

የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ለኢትዮጵያና ለእኛ ለንጉሠ ነገሥቷ ከፍተኛ ባለውለታችን ነው። ሙሶሊኒ በጦር በወጋን ጊዜ በገኔቭ የመንግሥታት ማህበር ላይ ለነፃነታችን ምን ያህል እንደተሟገተልን ምንጊዜም አንረሳውም። አሁንም ደጋግመን እንደተናገርነው፤ ፋሽስት ከአገራችን ተባርሮ ነፃነታችንን ያገኘነው፤ በታላቋ ብሪታንያ መንግሥት እርዳታ ነው ብለን፤ ደስታችንንና አድናቆታችንን ከመግለጥ አልተቆጠብንም። አዲስ አበባም በገባንበት ዕለት ለሕዝባችን ባደረግነው ንግግር፤ የቃል ኪዳን ወዳጃችን የእንግሊዝ መንግሥት ያደረገልንን ውለታ በሚገባ ካስረዳን በኋላ፤ " ... እንግሊዞችን እንደዘመድና ወዳጅ ተመልክታችሁ፤ ደግነትና ቸርነት እንድታሳይዋቸው አደራ እላችኋለሁ ... " ብዬ ተናግሬአለሁ። ሕዝቡም እኔ ንጉሠ ነገሥቱ የነገርኩትን በጥንቃቄ አዳምጦ፤ እንግሊዞች ነፃነታችንን እና ንጉሠ ነገሥታችንን ይዘውልን መጥተዋል በማለት፤ ደስታውንና ፍቅሩን በጋለ መንፈስ መግለጥ ጀምሮ ነበር። ነገር ግን ሳይውል ሳያድር ወዲያውኑ፤ የእንግሊዞች ወታደራዊ አስተዳዳሪዎች በሕዝቡ ላይ የሚያሳዩት የንቀት አስተያየት፤ ቀድሞ ፋሺስቶቹ ከሚያደርጉት የተለየ ካለመሆኑም በላይ፤ የአገሪቱ አመራር ሥልጣን በሙሉ ተጠቃልሎ በእንግሊዞች እጅ ብቻ የሚገኝ መሆኑን ሕዝቡ በግልጽ እንዲረዳው፤ የሚቻላቸውን ሁሉ በማድረግ ላይ ይገኛሉ። በዚህ ሁኔታ የእኛ ባንዲራችንን ሰቅለን፤ በቤተመንግሥታችን ባዶ ወንበር ይዘን መቀመጥ፤ ለሕዝባችን ምን ትርጉም ይኖረዋል? ... ብለን ማሰብ ጀምረናል።

ይህች በፋሽስት የተጠቃችና ከዓለም መንግሥታት ፍርድ የተነፈጋት አገራችን ኢትዮጵያ፤ አለች! አልሞተችም! እያልን በዚያ በመከራው ዘመን ያንን ሁሉ ትግል ያደረግነውና በመጨረሻውም በጦር ሜዳ ተዋግተን ያስገኘነው ድል፤ ውጤቱ የጣልያን ከሎኒ መባልና ለኮሎኒዎች በተመደበው አስተዳደር ውስጥ እንድንኖር መገደድ ከሆነ፤ ለነፃነታችን ገና ወደፊት ብዙ መሥዋዕትነትን መቀበል ይጠይቀናል ማለት ነው። ቀደም ሲል ለረዳትዎ ለብርጋድየር ለሽ እንደተናገርኩት ሁሉ ለእርስዎም የምገልጽልዎ፤ መላው የኢትዮጵያ ሕዝብና እኔም ንጉሠ ነገሥቱ፤ የታላቋ ብሪታንያን መንግሥት ውለታ ከልብ የምናስብና ወዳጅነታችንም እየጠነከረ እንዲሄድ አጥብቀን የምንፈልግ መሆናችንን ነው። ይሁን እንጂ፤ እርስዎም እንደሚያውቁት በዚህ ዓለም በሁለት መንግሥታት ሆነ ወይም በሁለት ሰዎች መካከል የሚገነባ ወዳጅነት የጋራ ጥቅምን በጋራ የሚጠብቅ እንጂ፤ አንዱ ለአንደኛው ተገዥ ሆኖ የሚኖር አይደለም። <u>በአሁኑ ሰዓት በሁለቱ አገሮቻችን መካከል የተፈጠረው አለመግባባት፤ ወዳጃችን የሆነው የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት፤ ነፃነታችንን ከፋሽስት እጅ እንድናስመልስ ከፍተኛ እርዳታ ካደረገልን በኋላ፤ ነፃነታችንን መልሶ በመውሰድ የራሱ ተገዥ እንዲያደርገን ስለማንፈልግ ነው።</u>

እንግዲህ! እርስዎም ልብ ብለው እንደሚያዩት፤ የታላቋ ብሪታንያ የጦር ካቢኔ በአገሬ በኢትዮጵያ ላይ ይህንን የሚያህል ከባድ ውሳኔ ሲያደርግ፤ በቅድሚያ ማወቅ ያለብኝ እኔ ንጉሠ ነገሥቱ መሆን ሲገባኝ፤ እንዴት ይኸ ችላ ተብሎ



ሰር ፊሊፕ ሚቼል
ለኢትዮጵያ ጉዳይ ዋና የፖለቲካ ሹም



ብሪጋድየር ሞሪስ ለሽ
ም/የፖለቲካ ሹም

ዜናውን በተዘዋዋሪ መንገድ እንድሰማው ይደረጋል? ... ይህንን በደል መቻውንም ልረሳው እንደማልችል ላረጋግጥልዎ እወዳለሁ። ... ከዚህ ሌላ እኛንና ኢትዮጵያውያን ሕዝባችንን ያስገረመንና ያሳዘነን አንድ ጉዳይ ሳልገልጽልዎ ሐሳቤን ማቆም አልፈልግም።

በደቡብ ግዛታችን በኩል ገሥግሶ ከእኛ በፊት መናገሻ ከተማችንን አዲስ አበባን የያዘው በገኔራል ካኒንግሐም የሚመራው ጦር፤ ግቡ የጠላታችንን ኃይል በቅድሚያ ለመደምሰስና በዋናው ከተማችን ላይ የነፃነታችንን መግቢያ በር ከፍቶ ሊጠብቀን ያሰበልን መስሎን፤ የጋለ ደስታችንንና አድናቆታችንን ገልጠን ነበር። ነገር ግን፤ የገኔራል ካኒንግሐም ጦር አዲስ አበባን ሲይዝ፤ እኛን ደብረማርቆስ ከተማ ታግደን እንድንቆይ ያስደረገው፤

1ኛ/ የእንግሊዝ ወታደራዊ ድርጅት የአገራችንን አመራር ሥልጣን በሚገባ ይዞ በየአውራጃው የአስተዳደሩን ሥርዓትና ሹማምንቶቹን ለመመደብ እንዲያመቸው፤

2ኛ/ የፋሽስት መንግሥት አገራችንን ከወረረበት ዕለት ጀምሮ፤ ከጣልያን አገር እያስመጣ ያከማቻቸውን የልዩ ልዩ ፋብሪካ ዕቃዎችንና በጠቅላላውም የኤሌክትሪክ መሣሪያዎችን፤ የከባድ ዕቃዎች ማጓጓዣ የሆኑትን ተሽከርካሪዎች በሙሉ እያስነሣ ወደ እንግሊዝ ቅኝ ግዛት ወደ ኬንያ ለመላክ እንዲያስችለው፤

መሆኑን ዘግይተን በተረዳን ጊዜ እጅግ አድርገን አዝነናል።

እንግዲህ! እስቲ እርስዎ ይህን ሁሉ በጽሞና ይመልከቱት? ... በእኛ በኢትዮጵያ ሕዝቦች ላይ ይህን የመሰለው በደል ሊደርስብን ይገባል ወይ? ... ጠላታችን ፋሽስት አገራችንን ይዞ ሀብታችንን እያሚጠጠ ከኖረ በኋላ፤ ጥሎት የሸሻቸውን ማናቸውንም ዕቃዎችና መሣሪያዎች መረከብና መጠቀም ያለብን እኛ ኢትዮጵያውያን መሆን አልነበረብንም ወይ? ... ደግሞስ! በኢትዮጵያ መሬት ላይ ከፋሽስት የተወረሰውን ተንቀሳቃሽ ሀብት በሙሉ ሰብስቦ ለቅኝ ግዛቶቹ ወስዶ ማስረከብ፤ ኢትዮጵያን ለመጉዳት ሆን ተብሎ የተወሰደ እርምጃ አይመስልም ወይ?

የተከበሩ ገኔራል!

እኔ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ንጉሠ ነገሥት፤ በኢትዮጵያ ሕዝብና በራሴ ስም ሆኜ የታላቋ ብሪታንያ የጦር ሹማምንቶች ከመንግሥታቸው በተሰጣቸው ሥልጣን እስካሁን የወሰዷቸው እርምጃዎች ምን ያህል ቅሬታዎች እንዳሳደሩብን ዘርዝሬ አስረድቼዎታለሁ። በእኛ በኢትዮጵያውያን አስተሳሰብ፤ በሁለት ወዳጆች መካከል ቅሬታ ሲፈጠር፤ መድኃኒቱ ተገላልጦ መነጋገር ነው ብለን እናምናለን። እኔም፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥትና ሕዝብ ጽኑ ወዳጅ መሆኔን እያረጋገጥኩ፤ በዚሁ የወዳጅነት መንፈስ ላይ ተመሥርቼ ያሉኝን ቅሬታዎች ሁሉ ዘርዝሬ እውነቱን ከመናገር አልተቆጠብኩም። እርስዎም በዚሁ መልክ ከልብዎ የሚያስቡትን ሁሉ እንደሚነግሩኝ ብዙ ተስፋ በማድረግ፤ ለማዳመጥ መዘጋጀቴን እገልጽልዎታለሁ።

# የፊሊፕ ሚቸል መልስ

" ... እኔ ዛሬ ለመጀመሪያ ጊዜ ጃንሆይን ለማየት ስመጣ፣ ጠላት የሆነው ፋሽስት ተባርሮ በአገርዎና በሕዝብዎ መካከል በመገኘትዎ፣ በከፍተኛ ደስታ ላይ አይዎታለሁ ብዬ ነበር። ነገር ግን፣ ግርማዊነትዎ በእኛ ላይ ብዙ ቅሬታዎች ይዘው ነው የጠበቁኝ። ሆኖም ጃንሆይ የሚያስቡትንና የታይዎትን ሁሉ ገልጸው ስለአስረዱኝ፣ ከልብ አመሰግናለሁ።

ጃንሆይ እንደጠቀሱት በወዳጆች መካከል አለመግባባት ሲፈጠር፣ ቅሬታዎችን ከማዳበር ይልቅ በቶሎ ተገላልጦ በመነጋገር መፍትሔውን ማግኘት ጠቃሚ መሆኑን ኢትዮጵያውያኖች ብቻ ሳይሆኑ፣ አብዛኛው የዓለም ሕዝብ እንደሚያምንበት እርግጠኛ ነኝ። እኔም በአገሬ በታላቋ ብሪታንያ መንግሥት የጦር ኃይሎች ስም ሆኜ የምገልጽልዎ ሐሳብ ሁሉ እውነትን በተመረኮዘ መንገድ ስለሆነ፣ ምናልባት በመጨረሻው ችግሮቻችንን አስወግደን ከመግባባት ደረጃ ሳንደርስ አንቀርም የሚል ስሜት ያድርብኛል። ለዚህም ግርማዊነትዎ ላነሷቸው ነጥቦች በበኩሌ የማውቀውንና የሚሰማኝን አስተያየት አቀርብልዎታለሁ።

1. የሁለተኛው የዓለም ጦርነት ከመጀመሩ በፊት፣ በስሕተት ይሁን ወይም በትክክል፣ ኢትዮጵያ የጣልያን ኮሎኒ ተብላ ታውቃለች። ስለዚህም፣ ይኸ ያለንበት የዓለም ጦርነት ሲፈጸም የሚደረገው የሰላም ጉባኤ፣ የኢትዮጵያ ነፃነት እንዲመለስ ውሳኔ እስከሚሰጥበት ጊዜ ድረስ፣ ፋሽስትን ከአገሪቱ የአባረረው የታላቋ ብሪታንያ ጦር በጊዜያዊ አስተዳደር ጠብቆ እንዲያቆያት መደረጉ በእኔ አስተያየት ለበጐ እርዳታ እንጂ፣ ለመበደል አይደለም። ሆኖም፣ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት የጦር ካቢኔው ያደረገውን ይህንን ውሳኔ፣ ግርማዊነትዎ ከፍ ካለ ኃዘን ጋር የማይቀበሉት መሆንዎን ለእኔም ለረዳቴም በግልጽ ስለአስረዱን፣ ነገ ወደ ሎንዶን ስሔድ ለበላዮቼ ከማቅረብ በስተቀር ሌላ በእኔ ሥልጣን የማሻሽለው ወይም የምቀንሰው ነገር የለም።

2. በጄኔራል ካኒንግሐም የሚመራው የደቡብ ጦር፣ በንጉሠ ነገሥቱ ከሚታዘዘው የጌዴዎን ኃይል ቀድሞ አዲስ አበባ የገባው፣ ጃንሆይ እንደተናገሩት የአስተዳደሩን ሥልጣን ተሸምቶ ለመያዝ እንዲመቸው ነው ተብሎ የተሰጠው አስተያየት ትክክል አይደለም። ካኒንግሐም አዲስ አበባን ሲይዝ፣ ለተወሰኑ ቀናቶች ግርማዊነትዎ ጉዞዎ እንዲቆዩ የተደረገው፣ የአገሩ ፀጥታ እስኪስተካከል ድረስ ነው እንጂ፣ ለሥልጣን ሽሚያ አልነበረም። ደግሞም በተጨማሪ በጃንሆይ የሚመራው የጌዴዎን ጦር ብቻውን ያንን ሁሉ የፋሽስት ኃይል ደምስሶ አዲስ አበባን መያዝ እንደማይችል መታወቅ ነበረበት።

ግርማዊነትዎ ደጋግሞ እንደተናገረው፣ የኢትዮጵያ አርበኞች ያደረጉት ተሳትፎና የፈጸሙት ጀግንነት፣ ፋሽስትን በአጭር ጊዜ ውስጥ ለማባረር እንዲቻል ምን ያህል እርዳታ እንደሰጠ የሚካድ አይደለም። ነገር ግን፣ በመላ ኢትዮጵያ ላይ የተንሰራፋውን የፋሽስትን ኃይል ለመሰባበርና ድልን ለመቀዳጀት የተቻለው፣ በታላቋ ብሪታንያ ጦር ኃይል መሆኑን ቅድሚያ መስጠት ያስፈልጋል። ስለዚህ፣ የታላቋ ብሪታንያ የጦር ኃይል፣ በያለበት የጠላትን ድርጅት እየነቀለ የሚይዛቸውን ግዛቶች በሥልጣን ማስተዳደር የሚጠበቅበት ኃላፊነትና ተግባር ነው። ይህም በጊዜአዊ

መልክ የሚሠራበት እንጂ፣ ለዘለቄታው ተይዞ የሚቀጥል አይደለም። ግርማዊነትዎ እንደሚያውቀው፣ ዛሬ ሁላችንም በዓለም ጦርነት አውድማ ላይ የምንገኝ መሆናችንን ማስብ ያስፈልጋል። በዚህ በጦርነት ዘመን ላይ ለሚያስፈልገው አስተዳደር፣ ሕጉ በፓርለማ እየተጠና የሕዝብ እንደራሴዎች ድጋፍ እያገኘ የሚፈጸም ነው ብሎ መጠበቅ አይቻልም። ይህ ዓይነቱ ዴሞክራሲያዊ ሥርዓት የሚካሔደው በሰላሙ ዘመን ብቻ ነው። አሁን ይህንን ምሳሌ የጠቀስኩልዎ፣ ካኒንግሐም አዲስ አበባ ሲገባ ማንንም ሳይጠይቅ ወዲያውኑ የአስተዳደሩን ሥልጣን ጠቅልሎ በመያዙ ግርማዊነትዎን ያስደነቀው፣ ጊዜው የጦር ዘመን እንጂ የሰላም ዘመን ባለመሆኑ ምክንያት ነው።

3. ግርማዊነትዎ የታላቋ ብሪታንያ የጦር ኃይል ጠላትን ድል እያደረገ በሚይዛቸው ግዛቶች ውስጥ፣ ፋሽስት ጥሏቸው የሸሸውን መሣሪያዎችና ዕቃዎች በሙሉ እየሰበሰበ ከኢትዮጵያ ውጭ ወደ ራሱ ግዛት አሻግሯቸዋል በማለት፣ ቅሬታዎን አሰምተዋል። በእንግሊዞች በኩል ይህ እርምጃ የተወሰደው በሕግ መሠረት መሆኑን ጃንሆይ እንዲያውቁት እፈልጋለሁ። በታላቋ ብሪታንያ ጦር ደንብ፣ በጦርነቱ ውስጥ ከጠላት የተወረሱትን ማናቸውንም ንብረቶች፣ መሣሪያዎችና ዕቃዎች ሰብስቦ ወደ አገሩ ለመላክ ሕጉ የሚፈቅድለት ስለሆነ፣ እስካሁን በኢትዮጵያ የተፈጸመውም በዚሁ መሠረት ነው። ... "

ጄኔራል ሚቸል ከዚህ በላይ የተገለጸውን መልስ ከሰጠ በኋላ፣ ዛሬ ማታ ከአዲስ አበባ ተነሥቼ ነገ በካርቱም በኩል ጉዞዬን ወደ ሎንደን ስለምቀጥል፣ ግርማዊነትዎ ለመንግሥቴ በተለይ የማቀርብልዎ ጉዳይ እንዳለ ይንገሩኝ ሲል ጠየቃቸው። ጃንሆይ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት እንዲያውቅላቸው ብቻ ሳይሆን፣ እንዲፈጽምላቸው የጠየቁት የሚከተሉትን ነበር።

" ... በንግግርዎ መጀመሪያ ላይ፣ በመካከላችን አንዳንድ የሐሳብ ልዩነቶች ቢኖሩም፣ በመጨረሻው ተግባብተን እንደምንለያይ ተስፋ አደርጋለሁ ብለው ነበር። ነገር ግን፣ እኔ እስከ መጨረሻው አድምጬ እንደተረዳሁት፣ በኢትዮጵያ ሕዝብና በራሴ ስም ሆኜ ከገለጽኩልዎ ዋና ዋና ጉዳዮች መካከል፣ አንዳቸውንም እስማማለሁ ወይም ለመደገፍ እሞክራለሁ አላሉም። ሆኖም አንዳንዱን ጉዳይ ለመንግሥትዎ እንደሚያቀርቡልን ተስፋ የሰጡት አለ። በዚህ መሠረት፣ በእኔ በኩል የታላቋ ብሪታንያን መንግሥት አጥብቄ የማሳስበው የሚከተሉትን ነው።

- ኢትዮጵያ በአሁኑ ሰዓት በታላቋ ብሪታንያ እርዳታና በአርበኞቿ ተጋድሎ ነፃነቷን ያገኘች ስለሆነ፣ የጣልያን ኮሎኒ ነች ወይም ነበረች የሚባለውን ጨርሶ አንቀበልም። የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ደህና አድርጎ እንደሚያውቀው፣ ፋሽስት የግፍ ጦርነት አካሒዶ አገራችንን ቢወራትም፣ በዓለም የመንግሥታት ማህበር የተወገዘና ይዞታውም ያልታወቀለት በመሆኑ፣ ኢትዮጵያ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባልነቷ አልተሠረዘም። ስለዚህ፣ ዛሬ ነፃነታችንን መልሰን ከያዝን በኋላ፣ እንደገና ተመልሰን የጣልያን ኮሎኒ ተብለን ልንሠየም አይገባም። እርግጥ ነው! ከሁለት ዓመታት በፊት በሚስተር ኔቪል ቻምበርሌን የሚመራው የእንግሊዝ መንግሥት፣ ሙሶሊኒን ከሂትለር ወዳጅነት ለማላቀቅና በኢስፓኝ የእርስ በርስ ጦርነት ውስጥ እንዳይካፈል ለማባበል፣ የኢትዮጵያን ይዞታ አውቆለት እንደነበረ ሁላችንም እናስታውሳለን። ሆኖም፣ የእንግሊዝ መንግሥት የወሰደው

እርምጃ በራሱ ስም ብቻ ነው እንጂ፣ በዓለም መንግሥታት ማህበር ስም አይደለም። ኢትዮጵያ፣ እንግሊዝ አባል በሆነችበት በሊግ ኦፍ ኔሽን ሕግ ነፃነቷ አልተነካም። ስለዚህ፣

1ኛ/ ኢትዮጵያ የጣልያን ኮሎኒ እንደሆነች ተቆጥራ በኮሎኒያሊስት አስተዳደር ውስጥ እንድትቆይ የጦር ካቢኔው ወስኗል የተባለው በአስቸኳይ እንዲሠረዝልን፣

2ኛ/ በኢትዮጵያና በእንግሊዝ መንግሥታት መካከል የሚደረገው የውል ስምምነት በአስቸኳይ እንዲዘጋጅልን፣

3ኛ/ በተቻለ ፍጥነት ኢትዮጵያ የጦር ሠራዊቷን ለማቋቋም እንድትችል የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት እርዳታ እንዲሰጠን፣

4ኛ/ ፋሽስትን ከአገራችን ለማስወጣት በተደረገው ጦርነት፣ ኢትዮጵያ ለእንግሊዝ መንግሥት የምትከፍለው ዕዳ ምን ያህል እንደሆነ እንዲገለጽልን፣

5ኛ/ በኢትዮጵያ የሠፈሩት የእንግሊዝ የጦር ወታደሮች በሕዝቡ ላይ የሚያሳዩት ንቀትና የኮሎኒያሊስት መንፈስ ከፍ ያለ ምሬት ስለፈጠረ፣ አስፈላጊው እርማት እንዲደረግልን፣

6ኛ/ ጠላት ሲሸሽ አገራችን ላይ የተዋቸውን መሣሪያዎችና ዕቃዎች የእንግሊዝ ጦር ኃይሎች እየሰበሰቡ ወደ ኬንያ ግዛታቸው የሚያሻግሩት ተገቢ አለመሆኑን ደጋግመን አስረድተን ነበር። እርስዎ እንደነገሩን የእንግሊዝ ወታደሮች ከጠላት እየተዋጉ የሚማርኳቸውን ንብረቶች ለመውሰድ ሕግ ይፈቅድላቸዋል ብለዋል። ነገር ግን የኢትዮጵያ አርበኞች ተዋግተው የማረኳቸውን የጠላት ንብረቶች፣ እንግሊዞች ለመውሰድ ሕግ ይፈቅድላቸዋል ማለት አይቻልም። ለምሳሌ ጅማ ላይ የነበረው የጠላት ጦር ድል ከሆነ በኋላ፣ በጦር አዝማቾችን በደጃዝማች ገረሱ ዱኪ የተማረኩትን የጠላት ንብረቶች የእንግሊዝ የጦር ኃይሎች ካልወሰድን በማለት ተኩስ ከፍተው አርበኞቻችንን ማቁሰላቸው ተመስክሮባቸዋል። ይህ ሁኔታ ወደፊት እንደማይደገም ተስፋ እያደረግን፣ በጠቅላላው በእኛ አስተያየት በአገራችን ላይ ጠላት ትቷቸው የሸሸውን ንብረቶች የምንረከባቸው እኛ ነን እንጂ፣ የእንግሊዞች ጦር መሆን የለበትም ብለን እናምናለን። በዚህ ጉዳይ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት የሚያደርገውን ቁርጥ ውሳኔ እንጠብቃለን።

ሜጀር ጀኔራል ፊሊፕ ሚቸል እ.ኤ.አ ግንቦት 23 ቀን 1941 ዓ.ም አዲስ አበባ መጥቶ ከንጉሠ ነገሥቱ ጋር ከዚህ በላይ የቀረበውን ሰፊ የሆነ የሐሳብ ልውውጥ ካደረገ በኋላ፣ ሎንደን ሔጄ የሚቻለኝን አስፈጽማለሁ ብሎ ተሰናብቶ ሔደ። በተለይ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አጥብቀው ያሳሰቡት በኢትዮጵያና በእንግሊዝ መንግሥታት መካከል የሚደረገው የስምምነት ውል እንዲፋጠን ነበር። ጄኔራል ሚቸል ለዚህ ውል ዝግጅት ስምንት ወራት ፈጅቶበታል። ይህን ያህል ጊዜ የፈጀው ምን ዓይነት ውል እንደሆነ በሚቀጥለው ምዕራፍ እናያለን።

# ምዕራፍ ፬

## ታሪካዊው የኢትዮጵያና የእንግሊዝ ውል

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ እ.ኤ.አ በሰኔ 1940 ዓ.ም ከሎንዶን ወደ ሱዳን መጥተው ከፋሽስት ጋር ለሚደረገው ውጊያ ዝግጅት በሚካሔድበት ጊዜ፣ ስለ ኢትዮጵያ ነፃነትና የመንግሥት አቋም ከታላቋ ብሪታንያ ጋር አንድ የስምምነት ውል እንዲፈረም፣ ለጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል እያከታተሉ በቴሌግራም ማሳሰባቸውን አላቋረጡም ነበር። እንደሚታወቀው፣ እንግሊዞች ከፋሽስት ጋር ለመዋጋት ቆርጠው የተነሡት፣ የሙሶሊኒ መንግሥት ከሂትለር ጋር ተሰልፎ ጦርነት ስለአወጀባቸው ነው እንጂ፣ ለኢትዮጵያ አዝነው ነፃነቷን ለማስመለስ አይደለም። በዚህ አኳኋን በእንግሊዞች የጦር ኃይል ፋሽስት ከኢትዮጵያ ግዛት ከተባረረ በኋላ፣ አገራችን ላይ ባሰፈሩት ጦር በመጠቀም፣ በቅኝ አስተዳደር ይዘው ያቆዩን ይሆናል በማለት ጃንሆይ በጣም ይሠጉ ነበር። ስለዚህም፣ ለነፃነታችን ዋስትና የሚሰጠን ስምምነት እናድርግ እያሉ አከታትለው ለላኳቸው ቴሌግራሞች፣ ጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል የሰጣቸው መልስ " ... በኢትዮጵያና በታላቋ ብሪታንያ መንግሥታት መካከል ውል ለማድረግ ያለንበት ጊዜና ሁኔታው አመች አይደለም ... " የሚል ስለሆነ፣ ጥርጣሬያቸውንና ሥጋታቸውን አልቀነሰላቸውም።

ሆኖም እ.ኢት.አቆ ሚያዝያ 27 ቀን 1933 ዓ.ም፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከመናገሻ ከተማቸው በገቡበት ዕለት፣ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት የኢትዮጵያን ነፃነት ለማስመለስ ያደረገውን ከፍተኛ እርዳታ በማመስገን ለዊንስተን ቸርችል ለላኩት ቴሌግራም፣ ጠቅላይ ሚኒስትሩ የሰጣቸው መልስ፣ ለኢትዮጵያ ነፃነት ጥሩ ምልክት መስሎ ታይቷቸው ነበር።

" ... የግርማዊነትዎን ወደ መናገሻ ከተማዎ በደህና መግባት፣ የታላቋ ብሪታንያ ሕዝብና መንግሥት የሰማው እጅግ ከፍ ባለና ዓለም አቀፍ በሆነ የደስታ ስሜት ነው። ከአገርዎና ከዙፋንዎ በመሰደድ የግፈኛው ፋሽስት ጥቃት የደረሰብዎ የመጀመሪያው ንጉሠ ነገሥት፣ በድል አድራጊነት ወደ አገርዎና ወደ ዙፋንዎ ለመመለስ የመጀመሪያው ሆነዋል። ከግርማዊነትዎ የተላከልኝ የምስጋና መልዕክት፣ ለታላቋ ብሪታንያ የጦር ኃይል አዛዦችና የኢትዮጵያን አርበኞች በመርዳት ጠላትን ለመደምሰስ ግዳጃቸውን ለፈጸሙት ወታደሮች እንዲደርስ ይደረጋል።

በታላቋ ብሪታንያ መንግሥት እና ሕዝብ ስም ሆኜ የክፉዎቹ ኃይል ጨርሶ እንዲደመሰስና የኢትዮጵያ ሕዝብ ሰላምና ብልጽግና እንዲያገኝ መልካም ምኞቴን አያይዛለሁ ... "

ዊንስተን ቸርችል
ጠቅላይ ሚኒስትር

እንግዲህ! ከዚህ በላይ የቀረበው የቸርችል ቴሌግራም በግልጽ እንዳሳየው፤ በኢትዮጵያ ነፃነትና በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዘውድ መመለስ ጉዳይ፤ ከእንግሊዞች ጋር ለጊዜው እንቅፋት ይፈጠር ይሆናል ብሎ ማሰብ የሚቻል አልነበረም፡፡ ነገር ግን፤ ንጉሠ ነገሥቱ ከመናገሻ ከተማቸው በገቡ አንድ ሳምንት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ፤ የአስተዳደሩን ሥልጣን ጨብጠው የቆይዋቸው የእንግሊዝ የጦር ሹማምንቶች፤ የኢትዮጵያ ነፃነት ገና ያላለቀለት ጉዳይ መሆኑንና ቀዳማዊ ኃይለሥላሴም የንጉሠ ነገሥት መንግሥታቸውን አቋቁመው ለመምራት ጊዜው አለመፍቀዱን ያስታወቋቸው፤ በዲፕሎማሲ ቋንቋ አልነበረም፡፡ እዚህ ላይ የደረሱት ሁኔታዎች በትክክል የሚያስረዱት፤ በኢትዮጵያ ነፃነት ጉዳይ በታላቋ ብሪታንያ መንግሥት የፖለቲካና የጦር መሪዎች መካከል ትልቅ ልዩነት የተፈጠረ መሆኑን ነው፡፡

የፖለቲካ መሪዎቹ ጠቅላይ ሚኒስትር ዊንስተን ቸርችልና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ አንቶኒ ኤደን፤ ገና ከመጀመሪያው ከሙሶሊኒ መንግሥት ጋር ጦርነት ማድረግ ሲገደዱ፤ በፋሽስት የተወረረችውን ኢትዮጵያን ነፃ ለማውጣት ያላቸውን ቅን አስተሳሰብ ከመግለጽ አልተቆጠቡም፡፡ በዚህም መሠረት ከፋሽስት ጋር ጦርነቱ በሚካሄድበት ወቅት፤ እ.ኤ.አ የካቲት 4 ቀን 1941 ዓ.ም የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ለፓርላማው በሰጠው መግለጫ፤ ታላቋ ብሪታንያ የኢትዮጵያን ነፃ መንግሥት ሆኖ መቋቋምና የቀዳማዊ ኃይለሥላሴንም መሪነት እንደምትቀበል፤ በተጨማሪም ታላቋ ብሪታንያ በኢትዮጵያ ላይ ምንም ዓይነት የግዛት ጥያቄ እንደማይኖራት በይፋ አስታወቀ፡፡

ጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል ደግሞ በበኩሉ፤ እ.ኤ.አ ሚያዝያ 9 ቀን 1941 ዓ.ም በተካሔደው የጦር ካቢኔ ስብሰባ ላይ ስለ ኢትዮጵያ ጉዳይ ተነሥቶ ንግግር ሲደረግ፤ " ... ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን አዲስ አበባ ወስዶ ወደ ዙፋናቸው እንዲመለሱ ማድረግ አይሻልም ወይ? ... "* የሚል ጥያቄ አቅርቦ ነበር፡፡ ነገር ግን የጦር መሪዎቹ እነ ጄኔራል ዌቨል፣ ፕላትና ካኒንግሃም በሰጡት መልስ፤ 1ኛ/ ንጉሠ ነገሥቱ አዲስ አበባ መሔድ የሚችሉት ፋሽስቶች በሙሉ አገሩን ከለቀቁና ፀጥታው አስተማማኝ ከሆነ በኋላ ነው፡፡ 2ኛ/ ንጉሠ ነገሥቱ ወደ ዙፋናቸው ከመመለሳቸው በፊት ሕዝቡ የሚቀበላቸው መሆን አለመሆኑን ማረጋገጥ ይኖርብናል የሚል የተጣመመ አስተያየት ስላቀረቡ፤ ጠቅላይ ሚኒስትሩ በሐሳቡ ሊገፋበት አልቻለም፡፡ እንደሚታወቀው የጦር መሪዎቹ ዓላማ፤ ፋሽስት ጨርሶ ከኢትዮጵያ ከወጣም በኋላ፤ ንጉሠ ነገሥቱ ወደ አገራቸው ቢመለሱም አገሪቱ በታላቋ ብሪታንያ ወታደራዊ አስተዳደር ተይዛ እንድትቆይና፤ የዓለም ጦርነት ከተፈጸመ በኋላ በሚደረገው የሰላም ጉባኤ የወደፊት ዕድሏ ቢወሰን ይሻላል የሚል ነው፡፡ በጦር ካቢኔው ውስጥ ይህንን ሐሳብ የሚደግፉት የጦር ሚኒስትሩና የጦር ኃይል መሪዎቹ፤ እንዲሁም የቅኝ ግዛት ጉዳይና የመንግሥት ንብረት ሚኒስትሮቹ ሲሆኑ፤ ሌሎቹ የሚተባበሩ አልነበሩም፡፡

እ.ኤ.አ ግንቦት 5 ቀን 1941 ዓ.ም ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መናገሻ ከተማቸው ከገቡ ከአሥር ቀናት በኋላ፤ በጦር ካቢኔው ላይ ስለ ኢትዮጵያ አስተዳደር ጉዳይ ተነሥቶ ንግግር ሲደረግ፤ ጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል የሚከተሉትን መምሪያዎች ሰጥቶ ነበር፡፡

* FO-371/27518

ሀ/ በኢትዮጵያ ውስጥ ያለውን የፋሽስት ጦር ጨርሶ መደምሰስና መሪውን ዱካ ዳ አስታን መማረክ፤

ለ/ በጣልያኖች ላይ ጭፍጨፋ እንዳይደርስ ብርቱ ጥንቃቄ ማድረግ፤

ሐ/ ድሉ እንደተገኘ ያለንን የጦር ሠራዊት ወደ ሌላው አስፈላጊ ቦታ ማዛወር፤

መ/ ኢትዮጵያን ለአገሪቷ መሪዎች አስረክቦ ቦታውን መልቀቅ፤ የወደፊት አስተዳደሯ በምን መልክ እንደሚሆን እኛ መጨነቅ የለብንም።*

ይህንን ከሚስተር ቸርችል የቀረበውን መምሪያ ሐሳብ፤ የጦር ሹማምንቶቹ ተቀብለው በተግባር ለማዋል የሚቻላቸው አለመሆኑን አስታወቁ። በዚህ በተፋፋመ የዓለም የጦርነት ወቅት፤ ኢትዮጵያን የሚያህል ስትራቴጂክ ቦታ ለቅቀን መውጣት አንችልም። እስከ ጦርነቱ ፍጻሜ ድረስ፤ የታላቋ ብሪታንያ ጦር ኢትዮጵያ ላይ መቆየትና የአገሩን አስተዳደር መቆጣጠር እጅግ አስፈላጊ ይሆናል። በዚህም መሠረት፤ የኢትዮጵያ ነፃነትና የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ወደ ዙፋናቸው መመለስ እንደተጠበቀ ሆኖ፤ ንጉሠ ነገሥቱ አገራቸውን ከወታደራዊው አስተዳደር ጋር እያስተባበሩና አስፈላጊም ሲሆን መምሪያውን እየተከተሉ የበኩላቸውን ተግባር ማከናወን ይኖርባቸዋል። ስለዚህ፤ ከጦር ካቢኔው ወደ መካከለኛው ምሥራቅ ጦር አዛዥ ወደ ጄኔራል ዌቨል የሚተላለፈው መምሪያ፤ ከዚህ በላይ በቀረበው ሐሳብ መሠረት እንዲሻሻል እንጠይቃለን ሲሉ የጦር ኃይል መሪዎቹ አመለከቱ።

እንደሚታወቀው፤ የዓለም ጦርነት በሚካሔድበት ወቅት የፖለቲካ መሪዎች በሚያደርጓቸው ውሳኔዎች ላይ የጦር ሹማምንቶቹ ለሚያቀርቡት አስተያየት ቅድሚያ ስለሚሰጡ፤ እነሱም ከፍተኛው ኃላፊነት የሚወድቀው እኛ ላይ ነው በማለት የሚፈልጉት ሁሉ እንዲፈጸምላቸው አጠንክረው ከመጠየቅ ወደኋላ አይሉም። በዚህም አኳኋን ጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል ግንቦት 15 ቀን 1941 ዓ.ም ባደረገው የጦር ካቢኔ ስብሰባ ላይ፤ " ... ኢትዮጵያን ለአገሯ መሪዎች አስረክቦ መውጣት እንጂ፤ ስለ ወደፊቷ አስተዳደር መጨነቅ የለብንም ... " ብሎ በሰጠው አስተያየት ላይ፤ የጦር ሹማምንቶቹ አንስማማም በማለት ያቀረቡለትን ተቃራኒ ሐሳብ ተቀብሎ እንዲፈጽሙት ፈቀደላቸው። የጦር ሹማምንቶቹ ባቀረቡት ሐሳብ መሠረት፤ ከጦር ካቢኔው የተፈቀደላቸው መምሪያ የሚከተለው ነበር።

" ... ታላቋ ብሪታንያ የኢትዮጵያ ነፃ መንግሥት ተመልሶ እንዲቋቋም ትቀበላለች። ነገር ግን ላለንበት የጦር ዘመን፤ የአገሪቱ አመራር በእንግሊዝ ወታደራዊ አስተዳደር ውስጥ እንዲቆይ ስለተወሰነ፤ ንጉሠ ነገሥቱ ከጦር ኃይል ባለሥልጣኖች የሚተላለፍላቸውን ምክርና አመራር እንዲከተሉ ይጠበቅባቸዋል ... "

በኮሎኒያሊስት መሠረታዊ አስተሳሰብ ሲሠሩ የኖሩትና በቂ ልምድ ያላቸው እነ ጄኔራል ፊሊፕ ሚቸል፤ የጦር ካቢኔው የሰጣቸውን ይህችን አረንጓዴ መብራት ይዘው "ሥልጣን በእንግሊዞች እጅ ብቻ" በማለት በኢትዮጵያና በታላቋ ብሪታንያ መካከል የሚደረገውን ውል እንደፈለጋቸው ቀላልፈው አዘጋጁት። በዚህ ውል ውስጥ የተጠቀሱት ዋና ዋናዎቹ አሳዛኝ ጉዳዮች የሚከተሉት ነበሩ።

---

* FO 371/27518



በቀዳማዊ ኃይለሥላሴና በሰር ፊሊፕ ሚቼል የተፈረመው፣ ኢትዮጵያን ወደ ሞግዚት አስተዳደር የሚመራው የግዴታ ውል፣
(እ.ኤ.አ ጥር 31/1942 ዓ.ም)

- ንጉሠ ነገሥቱ ስለ ኢትዮጵያ ጉዳይ በማናቸውም መስክ፣ የእንግሊዝ ወታደራዊ አስተዳደር ከሚሰጣቸው መምሪያ ውጭ በራሳቸው ሐሳብ የሚወስኑት አንዳች ነገር የለም።

- ንጉሠ ነገሥቱ እንግሊዞቹን ሳያማክሩና እነሱም ሳይስማሙበት፣ በየሥራው ዘርፍ ሰዎች ለመደልደልና ለመሾም አይቻላቸውም።

- ሕዝቡ ለመንግሥት የሚከፍለውን ታክስና ግብር ለመተመንና ለመሰብሰብ፣ ከዚያም ለየአስፈላጊው ሥራ የገንዘብ ወጭ ለማድረግ ሥልጣኑ የእንግሊዞች ነው።

- የፖሊስ ሠራዊትን የሚያቋቁሙና ከሚሾኑንም ሾመው የሚመሩት እንግሊዞች ናቸው።

- የከፍተኛና የጠቅላይ ፍርድ ቤቶች ሰብሳቢ ዳኞች የሚሆኑትን የሚሠይሙት እንግሊዞች ናቸው። ተሿሚዎቹም የእንግሊዝ ዜጎች መሆን አለባቸው። የውጭ አገር ዜጎች ክስ የሚደረገውና ፍርዱ የሚታየው በእንግሊዞች ዳኝነት ብቻ ነው።

- ንጉሠ ነገሥቱ ከእንግሊዞቹ ጋር ስምምነት ሳያደርጉ በራሳቸው ሥልጣን የጦር ሠራዊት ለማቋቋምና ዘመቻም ለማካሄድ አይፈቀድላቸውም።

- በኢትዮጵያ ያሉትን፣ የፈረንሣይና የኢትዮጵያ የምድር ባቡር ኩባንያ፣ የፖስታ፣ የቴሌፎንና የቴሌግራም ድርጅቶችን የማስተዳደር ሥልጣን የእንግሊዞች ነው።

- ለኢትዮጵያ የሚሾመው የታላቋ ብሪታንያ የዲፕሎማቲክ ሚሲዮን መሪ፣ ከሌሎቹ አገሮች ዲፕሎማቶች ሁሉ የፕሮቶኮል ተቀዳሚነት ይሰጠዋል። ሌሎች በውሉ ውስጥ ያልተጠቀሱ ሕገወጥ የሆኑ የዲፕሎማቲክ ሥርዓቶች ነበሩ። እነዚህም አንደኛው፣ የእንግሊዝ የዲፕሎማቲክ ሚሲዮን መሪ (ማለት ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትሩ) አዲስ አበባ ሲገባ፣ አውሮፕላን ጣቢያ ተገኝቶ የሚቀበለው የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ መሆን አለበት ብለው እንግሊዞቹ ስላስገደዱ፣ በዚህ አኳኋን ለጥቂት ጊዜ ሲፈጸም ቆይቷል። ሁለተኛው፣ ከእንግሊዝ መንግሥት ጋር ላለው የሥራ ግንኙነት የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ እንግሊዝ ለጋሲዮን ድረስ እየሄደ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትሩን እንዲያነጋግር ተደርጎ ነበር።

እነዚህ ከዲፕሎማቲክ ሥርዓት ውጭ ሕገ ወጥ የሆኑት የኮሎኒያሊስት አሠራሮች የተወገዱት፣ እ.ኤ.አ በ1944 ዓ.ም የሁለቱ ዓመት የውል ዘመን ከተፈጸመ በኋላ ነው።

እንግዲህ ከዚህ በላይ ዋና ዋናዎቹ ግዴታዎች እንደተገለጹት፣ በአሥራ ሁለት አንቀጾች ተቆላልፎ የተዘጋጀው የእንግሊዞች የሁለት ዓመት የግዴታ ውል፣ የኢትዮጵያን መንግሥት እንደገና ተመልሶ መቋቋምና የንጉሠ ነገሥቱን ወደ ዙፋናቸው መመለስ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት መቀበሉን ከማረጋገጡ በስተቀር፣

የአገሩ አስተዳደር በሙሉ ሥልጣን የተያዘው በእንግሊዝ ወታደራዊ ድርጅት እጅ መሆኑን ነው። ጄኔራል ሚችል ለስምንት ወራት ሲተበትብ የቆየበትን ይህንን ውል፤ ንጉሠ ነገሥቱ እንዲፈርሙ ሲያቀርብላቸው፤ ምን ያህል እንደተማረሩና ምን ያህል እንደተበሳጩ በዚያን ሰዓት አጠገባቸው የነበሩት ሰዎች ሁሉ የሚያስታውሱት፤ ከፍተኛ በሆነ የሐዘን ስሜት ነው። በዚያን ጊዜ የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር የነበሩት አቶ ጌታሁን ተሰማ እንደነገሩኝ፤ የፊርማው ሥነ ሥርዓት ከመከናወኑ በፊት (31/01/42) ጃንሆይ መሳፍንቱንና ሚኒስትሮቹን ሰብስበው ያደረጉት ንግግር የሁሉንም የአገር ፍቅር ስሜት የሚቀሰቅስ ነበር።

" ... ሁላችሁም እንደሰማችሁት፤ በዛሬው ዕለት ጥር 23 ቀን 1934 ዓ.ም፤ ከታላቋ ብሪታንያ ጋር ስለሚኖረን ግንኙነት የሁለት ዓመት ዕድሜ ያለው ውል እንድንፈራረም ግዴታ ሆኖብናል። ግዴታ የምንለው ውል ለምን አስፈለገ? ለማለት አይደለም። ገና በጦር ሜዳ በነበርን ጊዜ፤ በሁለቱ አገሮቻችን መካከል አንድ ዓይነት የስምምነት ውል ብናደርግ፤ ነፃነታችንን ከተረከብን በኋላ አንዳች ችግር እንዳይፈጠር ይረዳናል እያልን በብርቱ ያሳሰብነው እኛ ነበርን። በዚያን ጊዜ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ውል የማድረጉ አስፈላጊነት ስላልታየው፤ ጥያቄያችንን ሳይቀበለው ቀረ። አሁን ፋሽስት ከአገራችን ከተባረረ በኋላ ነፃነታችን ሲመለስ፤ ስለ ግንኙነታችን በውል እንድንስማማ በድጋሚ ያቀረብንላቸውን ጥያቄ ተቀብለው፤ እኛ አዘጋጅተን እናመጣለን የሚል ቃል ሰጥተውን ስንጠባበቅ፤ ስምንት ወራት አልፏ ነበር። አሁን ከዚህ ሁሉ ጊዜ በኋላ አዘጋጅተው ያቀረቡልንን ውል ስንመለከተው፤ የዓለም ጦርነት እስከሚፈጸም ድረስ ለሚቀጥሉት ሁለት ዓመታት የታላቋ ብሪታንያ የጦር ኃይል ኢትዮጵያን ይዞ መቆየት ስለአለበት፤ በአገራችን አስተዳደር ላይ ሙሉ ሥልጣን እንዲሰጠው የሚጠይቅ ነው። እርግጥ ነው! በዚህ ውል ውስጥ በመጠኑም ቢሆን የሚያረካን አንድ ነገር መኖሩ አይካድም። ይኸውም፤ የኢትዮጵያ ነፃ መንግሥት ተመልሶ መቋቋሙንና የንጉሠ ነገሥቱንም ወደ ዙፋን መመለስ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት መቀበሉን የሚያረጋግጥ መሆኑ ነው። ሌላው የሕዝባችንን አስተዳደር በሚመለከቱት ዋና ዋና ጉዳዮች ላይ ሥልጣኑ በእንግሊዞቹ እጅ ስለሆነ፤ እኛ የእነሱን ስምምነት ሳናገኝ ምንም ነገር እንደምንፈልገው ለመሥራት ባለመቻላችን እጅግ አድርጎ አሳዝኖናል። በኢትዮጵያ ታሪካችን ይህን የመሰለ የውጭ እጅ ጫና ደርሶብን ስለማያውቅ፤ እኔ በበኩሌ የቀረበልንን ውል አልፈርምም ብዬ በሚደርሰው ሁሉ መሥዋዕትነትን ለመቀበል መዘጋጀት እችል ነበር። ነገር ግን ይህንን እርምጃ ብወስድ፤ የኢትዮጵያን ሕዝብ ለእንግሊዞች ፍጹም ተገዥነት አሳልፎ ከመስጠት በስተቀር፤ ነፃነቱን የማድንለት መከላከያ የለኝም። ስለዚህም ከሁሉ በፊት የናንተን ሐሳብና አስተያየት መስማት አስፈላጊነቱ ይታየኛል። ከዚያ በኋላ የሚበጀውን እኔ እወስናለሁ። ... "

ጃንሆይ ንግግራቸውን ሲፈጽሙ ያደረባቸውን ብስጭት መግታት ስለአቃታቸው፤ በስብሰባው ላይ የተካፈሉት መሳፍንትና መኳንንት ሁሉ መደንገጣቸው ይታይ ነበር። በዚህ ጊዜ ራስ ካሣ ብድግ ብለው ያደረጉት ንግግር እንኳንስ የተሰበሰቡትን ሰዎች፤ ጃንሆይንም ወደ መልካምና የጠነከረ መንፈስ የሚለውጥ ሆነ።

" ... ጃንሆይ! ይህንን ያህል ቅሬታና ምሬት ያደረብዎ፤ የኢትዮጵያ ሕዝብ ከጣልያን ገዥነት ነፃ ወጣ ከተባለ በኋላ፤ የእንግሊዝ ባለሥልጣኖች ለምን መጡብን? ብለው ነው። ሁላችንም ልብ ብለን ብናየው፤ የሁለቱም ፈረንጆች አመጣጥ የተለያየ ነው። ጣልያኖች ተዘጋጅተው የመጡት የኢትዮጵያን ሕዝብ

ለዘለ ዓለሙ ቀጥቅጠን እንገዛዋለን፤ የአገሩንም ሀብት አሟጠን እንበላለን ብለው ነው። ዛሬ ደግሞ ጣልያን ከተባረረ በኋላ እንግሊዞች የመጡብን፤ የዓለም ጦርነት እስከሚያልቅበት ጊዜ ድረስ አገራችሁን ይዘን መቆየት ስለሚያስፈልገን፤ ለሁለት ዓመት የአስተዳደሩን ሥልጣን እኛ እንያዘው ብለው ነው። እንግዲህ! እዚህ ላይ ሁላችንም እንደምናየው፤ እንግሊዞች የሁለት ዓመት የአስተዳደር ሥልጣን የጠየቁት በወግና በጨዋ ደንብ ሲሆን፤ ይህንንም ፈቅደው የሚሰጧቸው የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ጃንሆይ ራስዎ ነዎት። በዚህ አኳኋን፤ እንግሊዞቹ ጃንሆይ በሚፈርሙላቸው ሰነድ ላይ፤ የተቀበልነውን የሁለት ዓመት ሥልጣን ጊዜው ሲያልቅ አስረክበን እንሄዳለን። በተጨማሪም ዛሬም ሆነ ነገ፤ የኢትዮጵያን ነፃ መንግሥትነትና የንጉሠ ነገሥቷን ዘውድ በወግ እናውቃለን ብለው፤ በታላቁ ማሕተማቸው ካረጋገጡልን፤ ምን ያሳስበናል? ምንስ ያስጨንቀናል? ... ጃንሆይ ቅድም ደህና አድርገው ተናግረውታል። ዛሬ በአለንበት የጦርነት ዓለም ውስጥ ከእንግሊዞች ጋር መጣላት፤ ይህችን በእግዚአብሔር ቸርነት ያገኘናትን አገራችንንና ነፃነታችንን ማስወሰድና ሕዝባችንን ለፈረንጆች ገዥዎች ማስረከብ ካልሆነ በስተቀር የምናስገኘው ጥቅም የለም ብለዋል። ይኸ የጃንሆይ አባባል ትክክለኛና እውነተኛ ነገር ነው። ጠብ የሚፈውስ መድኃኒት ስለማይገኝ፤ ትግላችንም ሆነ ሙግታችን በዘመን አመጣሹ ጠባይ በመነጋገርና በመወያየት ሊከናወን ይችላል። ስለዚህ፤ በራሴም ሆነ እዚህ በተሰበሰቡት ሰዎች ስም ሆኜ ጃንሆይን አጥብቄ የማሳስበው፤ ብስጭትን አርቀው፤ የሰላም መንፈስዎን አድሰው፤ እንግሊዞች የጠየቁዎትን ውል በማጽደቅ፤ ለመላው ሕዝብዎ ችግሮችን አስወግደው ደህንነትን እንዲያስገኙለት ትዕግሥትዎን ከመቸውም ጊዜ ይበልጥ እንዲያጠነክሩት ነው። ... "

ይህ የራስ ካሣ ኃይሉ ንግግር፤ ጃንሆይን በአንድ ጊዜ ከተስፋ መቁረጥ ወደ ተስፋ ማሳደር ለወጣቸው። በስብሰባው ላይ የተካፈሉትም መሳፍንትና መኳንንት በዚህ በራስ ካሣ ንግግር እጅግ ተደስተው፤ የእሳቸው ቃል ቃላችን ነው እያሉ፤ ንጉሠ ነገሥቱ የቀረበላቸውን ውል እንዲፈርሙ ያለ አንዳች ቅሬታ መስማማታቸውን ገለጹላቸው።

በዚህ መሠረት፤ እ.ኤ.አ ጥር 31 ቀን 1942 ዓ.ም፤ እ.ኢ.ት.አቆ ጥር 23 ቀን 1934 ዓ.ም ከእኩለ ቀን በኋላ፤ በጄኔራል ፊሊፕ ሚቸል የተዘጋጀውን ውል ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከጄኔራል ሚቸል ጋር ሆነው በንጉሠ ነገሥት ፊርማቸው አጸደቁት።

መረጃዎች፤ በግዴታ ስለተፈረመው የመጀመሪያው ውል
- FO 371/27524
- FO 371/27522
- FO 371/31597
- FO 371/35611
- FO 371/27525

# ምዕራፍ ፩

## ከእንግሊዞች ለመላቀቅ፤ ድጋፍ ፍለጋ ወደ አሜሪካ

እ.ኤ.አ ጥር 31 ቀን 1942 ዓ.ም በታላቋ ብሪታንያና በኢትዮጵያ መካከል በተፈረመው ስምምነት የአገሪቱ አስተዳደር ሥልጣን፤ በእንግሊዞች እጅ ብቻ እንዲሆን ያስደረገ ስለሆነ፤ የዚህ የሁለት ዓመት የውል ዘመን ሲፈጸም በተመሳሳይ መልኩ እንዳይደገም ወይም እንዳይራዘም፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴና መንግሥታቸው፤ መከላከያውን አዘጋጅቶ ለመጠበቅ ብርቱ ጥረት ማድረግ ነበረባቸው። በዚያን ዘመን ካሉት ታላላቅ አገሮች መካከል፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ወታደራዊ ድርጅት በኢትዮጵያ ላይ አለአግባብ የያዘውን የአስተዳደር ሥልጣን ተመልክቶ፤ "ልክ አይደለም" ብሎ መናገር የሚችል፤ ከዩናይትድ ስቴትስ ኦፍ አሜሪካ በስተቀር ሌላ መንግሥት አልነበረም።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ከሆኑበት ጊዜ ጀምሮ፤ ከአሜሪካ መንግሥት ጋር የወዳጅነት ግንኙነት ለመዘርጋትና ለማስፋፋት የተቻላቸውን ሁሉ ከማድረግ አላቋረጡም ነበር። በተለይም ፍራንክሊን ዲ ሩዝቬልት (Franklin D.Roosevelt) እ.ኤ.አ በ1932 ዓ.ም የአሜሪካ ፕሬዚዳንት ሆኖ ከተመረጠ ከአንድ ዓመት በኋላ፤ የልጃቸው የልዕልት ተናኘወርቅ ኃይለሥላሴ ባለቤት የሆኑትን ራስ ደስታ ዳምጠውን ወደ ዋሽንግተን ዲ.ሲ. ልከው፤ ልዩ መልዕክትና ገጸ በረከት ለፕሬዚዳንቱ እንዲያቀርቡ አድርገዋል። ጃንሆይ ለሩዝቬልት የላኩት ልዩ መልዕክት፤ በሁለት ዋና ዋና ጉዳዮች ላይ ያተኮረ ነበር።

የመጀመሪያው፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ኢትዮጵያን ለመምራት የንጉሠ ነገሥትነትን ዘውድ ከጫኑበት ዕለት ጀምሮ፤ ሕዝቡን ወደ ዘመናዊ ሥልጣኔ ለማሸጋገር መሠረቱ ትምህርትን ማስፋፋት ስለሆነ፤ የአገሪቱ አቅም በሚፈቅደው መጠንና ከወዳጅ መንግሥታትም በሚገኘው እርዳታ፤ የሚቻላቸውን ሁሉ በተግባር ለመግለጽ ቆርጠው የሚሠሩ መሆናቸውን፤ የዩናይትድ ስቴትስ ኦፍ አሜሪካ እንዲያውቅላቸው፤

ሁለተኛ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከአንዳንድ የታመነ ምንጭ በሚደርሳቸው መረጃ፤ የጣልያን ፋሽስት መንግሥት፤ በ1896 ዓ.ም አድዋ ላይ አገራችንን ለመውጋትና ለመያዝ መጥቶ የደረሰበትን ውርደት ለመበቀልና ኢትዮጵያን ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ ጦር የሚያዘጋጅ ስለሆነ፤ ለአገሮች ነፃነትና መብት የሚታገለው የአሜሪካ መንግሥትና ሕዝብ፤ ኢትዮጵያን ለነፃነቷ እንዲያስብላት አደራ ለማለት ነው።

ራስ ደስታ ዳምጠው፤ በኢትዮጵያዊው ሐኪም በዶክተር መላኩ በያን አስተርጓሚነት፤ ይህንን የንጉሠ ነገሥቱን መልዕክት ለአሜሪካው ፕሬዚዳንት ካቀረቡ በኋላ፤ ሩዝቬልት በጃንሆይ መልዕክተኛ ላይ ከፍተኛ ግምት በማሳደር፤ ዋሽንግተንን ለቅቀው ወደ አገራቸው ከመመለሳቸው በፊት፤ በዋይት ሐውስ ቤተመንግሥት ስለክብራቸው የምሳ ግብዣ አድርጎ አስናብቷቸዋል። ከጥቂት

ዓመታት በኋላ ራስ ደስታ ዳምጠው ለአገራቸው ነፃነት ከፍተኛ ተጋድሎ በማድረጋቸው፣ በጨካኞቹ ፋሽስቶች እጅ መገደላቸውን ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት የሰማው ዘግይቶ በቅርብ ጊዜ ውስጥ ስለሆነ፣ እጅግ አዝኖ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የሚከተለውን የሐዘን መግለጫ ላከላቸው።

ወዳጄ ንጉሠ ነገሥት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ!

እ.ኤ.አ 1933 ዓ.ም የግርማዊነትዎ አማች የሆኑትን እጅግ የተከበሩ ራስ ደስታ ዳምጠውን በዋይት ሐውስ ተቀብያቸው እንደነበረ ሁልጊዜ አስታውሳለሁ። አሁን በመጨረሻ እንደሰማሁት እኚህ ታላቅ ሰው ለአገራቸው ነፃነት ሲዋጉ በነበሩበት ዘመን፣ በጨካኞቹ ፋሽስቶች መገደላቸውን ሰምቼ እጅግ አዘንኩ። ራስ ደስታ በጣም የሚደነቁና የሚከበሩ ታላቅ ሰው ናቸው። ከእሳቸው ጋር በልዩ ልዩ ጉዳዮች ላይ ሐሳብ ለመለዋወጥ ያጋጠመኝን ዕድል በጥልቅ ስሜት እያስታወስኩ፣ በከፋዎች እጅ በመገደላቸው ከፍ ያለውን ሐዘኔን ለግርማዊነትዎ እገልጽልዎታለሁ።

ወዳጅዎ ፍራንክሊን ዲ ሩዝቬልት

በጠላት ዘመን የአሜሪካ መንግሥት እጅግ ጥብቅ በሆነ የገለልተኛነት ፖሊሲ የሚመራ ስለነበረ፣ ኢትዮጵያ በፋሽስት ተወራ ብርቱ ጥቃት በደረሰባት ጊዜ፣ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት የሙሶሊኒን መንግሥት ይዞታ እስከ መጨረሻው አላውቅም ከማለት በስተቀር፣ ሌላ እርዳታ ለማድረግ አልተቻለውም። ይሁን እንጂ፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በስደትም ላይ ሆነው ጨካኙ ፋሽስት በኢትዮጵያ ሕዝብ ላይ የሚፈጽመውን ግፍ ለአሜሪካው መሪ ከማሳሰብ አላቋረጡም ነበር። ሁለቱ መሪዎች በኮሬስፖንዳንስ ግንኙነታቸው ላይ ችግር የተፈጠረው፣ ፋሽስት ከኢትዮጵያ ተባርሮ እንግሊዞች በጦር ኃይላቸው አገራችንን በሥልጣን ማስተዳደር ከጀመሩበት ቀን አንሥቶ ነው። ምክንያቱም፣ ከኢትዮጵያ የሚላኩትንም ሆነ ወደ ኢትዮጵያ የሚመጡትን የውጭ አገር መልዕክቶች፣ እንግሊዞች ብርቱ ቁጥጥር ስለሚያደርጉ ነው። በተለይም ንጉሠ ነገሥቱ የታላቋ ብሪታንያ የጦር አስተዳደር የሚያደርስባቸውን ችግር ለወዳጅ መንግሥታት ለማስታወቅ እንዳይችሉ፣ የፖስታውንና የቴሌግራሙን መስመር ዘግተውባቸው ነበር። በዚህ አኳኋን፣ ጃንሆይ ከዩናይትድ ስቴትስ ኦፍ አሜሪካ ጋር በቅድሚያ የዲፕሎማቲክ ግንኙነት ለመክፈት ያሰቡትን እንዳይፈጽሙ እንግሊዞች በሩን ስለዘጉባቸው፣ ለሁለት ዓመታት ያህል ከተሠቃዩ በኋላ፣ አንድ የኢትዮጵያን ልዩ መልዕክተኛ ወደ ዋሽንግተን ለመላክ የሚያስችል ዕድል አጋጠማቸው።

ይኸውም፣ እ.ኤ.አ በሰኔ ወር 1943 ዓ.ም በአሜሪካን አገር በቨርጂኒያ ከተማ በተዘጋጀው የዓለም የእርሻና የምግብ ድርጅት ጉባኤ ላይ፣ ኢትዮጵያ እንድትካፈል ከሁለት ወራት በፊት የጥሪው ደብዳቤ ከጃንሆይ ልዩ ጽሕፈት ቤት ደረሰ። ወዲያው ንጉሠ ነገሥቱ አቶ አክሊሉ ሀብተወልድን በዚያን ጊዜ የጽህፈት ም/ሚኒስትርና የሕግ አማካሪ ጠርተው፣ ጉዳዮን አጥንተው ሐሳብ እንዲያቀርቡ አዘዟቸው። ይህ ለኢትዮጵያ በቴሌግራም የተላከው ጥሪ አዲስ አበባ ሲደርስ፣ በቅድሚያ ያዩት ባለሥልጣኖቹ እንግሊዞች ቢሆኑም፣ ኢትዮጵያ የእርሻ አገር መሆኗ የታወቀ ስለሆነ፣ በዚህ ጉባኤ ላይ ተካፋይ እንዳትሆን ምንም ዓይነት ተንኮል መፍጠር አልፈለጉም።

በግርማዊነታቸው ቢሮ፤ ክቡር ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የጽሕፈት ሚኒስትር፤ ክቡር አቶ መኰንን ሀብተወልድ የእርሻ ሚኒስትር፤ ብላታ ኤፍሬም ተወልደ መድህን የውጭ ጉዳይ ም/ሚኒስትር በተገኙበት፤ የሕግ አማካሪው አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ በታዘዙት መሠረት፤ ስለ ቨርጂኒያው ስብሰባ የሚከተለውን ሐሳብ አቀረቡ።

አክሊሉ፤ እ.ኤ.አ በሰኔ ወር 1943 ዓ.ም መጀመሪያ ሳምንት ላይ፤ በአሜሪካን አገር በቨርጂኒያ (Virginia) በሚደረገው የዓለም የእርሻና የምግብ ጉዳይ ጉባኤ ላይ፤ ኢትዮጵያ ተካፋይ እንድትሆን ጥሪው መድረሱ በጣም ጠቃሚ ነው። ስለዚህም ኢትዮጵያ የተላከላትን ጥሪ መቀበሏን፤ በዛሬው ዕለት ማስታወቅ ይኖርብናል። በደንቡ መሠረት በዚህ ጉባኤ ላይ የግርማዊነትዎ መልዕክተኛ ሆኖ መሔድ የሚገባው፤ የእርሻ ሚኒስትሩ ነው። ነገር ግን፤ እኔ አንድ የተለየ ሐሳብ ለማቅረብ እንዲፈቀድልኝ እለምናለሁ። ይኸውም፤ ይህንን ጥሩ አጋጣሚ ለመጠቀም፤ ዋና መልዕክተኛ ሆኖ ወደ ዋሽንግተን የሚሔደው የግርማዊነትዎ ምክትል የገንዘብ ሚኒስትር አቶ ይልማ ዴሬሣ እንዲሆንና፤ አሜሪካ በሚቆይበትም ጊዜ የሚከተሉትን ዋና ዋና ጉዳዮች ለመፈጸም የተቻለውን እንዲያደርግ ነው።

1ኛ/ ከሁለት ዓመታት በፊት፤ የአሜሪካ ኮንግረስ ለፕሬዚዳንት ሩዝቬልት በሰጠው ልዩ ሥልጣን፤ ሌንድ ሊዝ (Lend Lease) በተባለው ፕሮግራም፤ የአሜሪካ ወዳጆችና ተባባሪዎች ለሆኑት አገሮች ሁሉ፤ የመከላከያ ኃይላቸውን እንዲገነቡ አስፈላጊውን እርዳታ ለመስጠት እንዲችል ፈቅዶለታል። አሁን እንደምንሰማው፤ በዚህ ሌንድ ሊዝ በተባለው ፕሮግራም የሚሰጠው እርዳታ፤ ለጦር መሣሪያዎች ጉዳይ ብቻ ሳይሆን፤ በኢኮኖሚም ልማት ረገድ አንዳንድ እርዳታዎችን ለመለገስና ለማበደርም እንዲቻል ተደርጓል። አቶ ይልማ ይህንን ጉዳይ ከእኔ በበለጠ ስለሚያውቀው፤ ዋሽንግተን በሚቆይበት ጊዜ ከአሜሪካ የኢኮኖሚና የፋይናንስ ባለሥልጣኖች ጋር በመነጋገር፤ ኢትዮጵያ በዚህ በሌንድ ሊዝ ፕሮግራም እንድትጠቀም ማስደረግ ይችል ይሆናል።

2ኛ/ የግርማዊነትዎ መልዕክተኛ የሚሆነው አቶ ይልማ ዋሽንግተን በሚቆይበት ጊዜ፤ የአሜሪካንን የፖለቲካ ሰዎች በማግኘት፤ "የዓለም ጦርነት እስከሚፈጸምበት ጊዜ ድረስ" በሚል ሰበብ፤ የእንግሊዝ ወታደራዊ አስተዳደር የሚያደርስብንን ችግር ለማስረዳት ዕድል ያጋጥመዋል የሚል ተስፋ አለኝ። በተጨማሪም ይህንን ጉባኤ ምክንያት በማድረግ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት የየአገሩን የመልዕክተኞች መሪዎች ተቀብሉ የሬሴፕሽን ግብዣ እንደሚያደርግላቸው በፕሮግራሙ ላይ ስለተጠቀሰ፤ አቶ ይልማ ዕድሉ ካጋጠመው ግርማዊነትዎ ለፕሬዚዳንት ሩዝቬልት የሚጽፉትን ደብዳቤ በእጅ ለማቅረብ ይችል ይሆናል ብዬ ተስፋ አደርጋለሁ።

3ኛ/ ግርማዊነትዎ ከዚህ ቀደም እንዳሰበው፤ ወደፊት ከእንግሊዞች ጋር ለምናደርገው ስምምነት ጥሩ ኤክስፒሪያንስ ያለው የሕግ አማካሪ ከአሜሪካ ለመቅጠር እንዲቻል፤ አቶ ይልማ ዋሽንግተን በሚቆይበት ጊዜ ባለሞያውን ለማስፈለግና ኢንተርቪዩ አድርጎ ለመወሰን ይመቸው

ይሆናል። በተጨማሪም ከዚህ ቀደም ግርማዊነትዎ እንዳሰበው፤ የጥቁር ተወላጆች ከሆኑት አሜሪካኖች በመምህርነትና በመሐንዲስነት ችሎታ ያላቸውን ለመምረጥና ቀጥሮ ለማስመጣት፤ አቶ ይልማ የተቻለውን ለማድረግ የግርማዊነትዎን መምሪያ መቀበል ይችላል።

ንጉሠ ነገሥቱ ከዚህ በላይ የቀረበውን የአቶ አክሊሉን ጥናት ካደመጡ በኋላ፤ የጽሕፈት ሚኒስትራቸው ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ፤ አስተያየት እንዲሰጡ ጠየቋቸው።

ጸ.ት ወልደጊዮርጊስ፤ " ... በአሜሪካን አገር በሚካሔደው የዓለም የእርሻና የምግብ ጉዳይ ጉባኤ ላይ፤ ኢትዮጵያ ተካፋይ እንድትሆን መጋበዟ በጣም የሚያስደስት ነው። የሕግ አማካሪም አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ የጠለቀ ጥናት በማድረግ፤ በዚህ ጉባኤ ላይ ምንም እንኳ የመልዕክተኞች መሪ መሆን የሚገባው፤ የእርሻ ሚኒስትርም ክቡር አቶ መኰንን ሀብተወልድ ቢሆንም፤ በዚህ ጉባኤ ሰበብ ሌሎች በጣም ጠቃሚ የሚሆኑትን ታላላቅ ጉዳዮች ለማከናወን የገንዘብ ም/ሚኒስትርም አቶ ይልማ ዴሬሣን መላክ ጥሩ ምርጫ መሆኑን እኔም እደግፋለሁ። በግርማዊነትዎ መልካም ፈቃድ አቶ ይልማ በዋሽንግተን ስለሚያከናውናቸው ዋና ዋና ጉዳዮች፤ አቶ አክሊሉ በሚገባ ዘርዝሮ ስለአቀረበው፤ በእኔ በኩል ተጨማሪ ሐሳብ የምሰጠው የለም። ሆኖም አቶ አክሊሉ ባቀረባቸው ዝርዝር ጉዳዮች ውስጥ፤ አቶ ይልማ ዕድል ያጋጠመው እንደሆን ግርማዊነትዎ ለፕሬዚዳንት ሩዝቬልት የሚጽፉትን ደብዳቤ በእጅ ለመስጠት ይሞክራል ብሏል። ይህ የሚሳካ ከሆነ፤ በጣም የሚያስደስት ይሆናል። ስለዚህ፤ ጃንሆይ ለወዳጅዎ ለአሜሪካ ፕሬዚዳንት በሚጽፉት ደብዳቤ ላይ የሚጠይቋቸው ሆኑ ወይም የሚጠቅሷቸው ዋና ዋና ጉዳዮች ምንና ምን መሆናቸውን አቶ አክሊሉ ሐሳብ እንዲሰጥ እጠይቃለሁ።

ጃንሆይ፤ አክሊሉ ተናገር!

አክሊሉ፤ ክቡር ጸሐፊ ትዕዛዝ ያነሡት በጣም ትልቁን ጉዳይ ነው። በእኔ አስተያየት የጃንሆይን ሐሳብ በሜሞራንደም መልክ አቶ ይልማ በእንግሊዝኛ አዘጋጅቶ ቢያቀርበው የተሻለ ይመስለኛል። በዚህ ሜሞራንደም የሚገለጹት ዋና ዋናዎቹ ሐሳቦች የሚከተሉት ቢሆኑ የሚጠቅሙ ይመስለኛል።

1ኛ/ ኢትዮጵያ ነፃነቷ ተመልሶ ግርማዊነትዎ ወደ መናገሻ ከተማዎ ከገቡበት ዕለት ጀምሮ፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት አገራችንን ከጠላት ተወስደው ከተያዙት ቅኝ ግዛቶች አንዷ እንደሆነች በመቁጠር፤ በእንግሊዝ ወታደራዊ አስተዳደር ተጨቁነን እንድንቆይ በግዴታ የፈረምነው ውል፤ በምን መልክ እንደሆነ ዋና ዋናዎቹን እንዘረዝራቸዋለን። ይህም ውል በመጭው ጥር ወር 1944 ዓ.ም የሚፈጸም ስለሆነ፤ የሚቀጥለው ስምምነታችን በሚዘጋጅበት ጊዜ በሁለቱ አገሮቻችን መካከል የጋራና የእኩልነት መብት እንዲመሠረት፤



ማዳም ሲልቪያ ፓንክረስት

የፋሽስት ጣልያን ኢትዮጵያን ለአምስት ዓመታት በግፍ ወርሮ ሕዝቦቿን በሚያስቃይበት ዘመን ብቻ ሳይሆን፤ እንግሊዞችም በሞግዚት አስተዳደር ለመጨቆን ሲነሱብን፤ እኚህ የታወቁ የሥነ ጽሑፍ ባለሞያ፤ ያለማቋረጥ ለአገራችንና ለሕዝባችን ነፃነት በመገናኛዎች ዘዴ የዓለምን መሪዎች ሕሊና ለመቀስቀስ ያደረጉት ተጋድሎ ምን ጊዜም በታሪካችን ሲታሰብ የሚኖር ነው።

ግርማዊነትዎ የጠበቀ ውሳኔ ያደረጉበት መሆኑን እናስረዳለን። ስለዚህም፣ ከታላቋ ብሪታንያ ጋር ለምናደርገው ድርድር፣ አንድ አሜሪካዊ የሕግ ባለሞያ እንዲሰጠን፣ የፕሬዚዳንቱን እርዳታ እንጠይቃለን።

2ኛ/ የኢትዮጵያ ወዳጅ ከሆነው ከዩናይትድ ስቴትስ ኦፍ አሜሪካ ጋር፣ ከጠላት በፊት የነበረውና በጠላት ዘመን የተቋረጠው የዲፕሎማቲክ ግንኙነታችን በተቻለ ፍጥነት ተመልሶ እንዲዘረጋ እናሳስባለን። ከእኛ በኩል ግርማዊነትዎ መርጦ የሚሾመውን ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር፣ አግሪመንቱን ለማግኘት አግባቡ ለሆነው ለአሜሪካ ስቴት ዴፓርትመንት በቅርብ ቀናቶች ውስጥ እንደምናቀርብ እንገልጻለን።

3ኛ/ በግርማዊነትዎ መሪነት፣ ኢትዮጵያ የዩናይትድ ስቴትስ ኦፍ አሜሪካ ታማኝ ወዳጅ ስለሆነች፣ <u>በዚህ ሌንድ ሊዝ (Lend Lease) ተብሎ በተሠየመው ለወዳጅ አገሮች በሚሰጥ የእርዳታ ፕሮግራም ኢትዮጵያ ለመጠቀም እንድትችል፣</u> የፕሬዚዳንቱን መልካም አስተያየት እንጠይቃለን።

4ኛ/ ኢትዮጵያ ካለፉት ሃምሳ ዓመታት ጀምሮ በኮሎኒያሊስቶች ኃይል ዙሪያዋን ተከባ፣ የባሕር በር እንድታጣ ተደርጎ በሥቃይ ስለምትኖር፣ ኮሎኒያሊስት ጣልያን ከነጠቃት ግዛቶቿ አንዷ የሆነችው "ኤርትራ" ወደ እናት አገሯ እንድትመለስ ግርማዊነትዎ በሚያደርገው ጥረት፣ የሩዝቬልት መንግሥት ድጋፍ እንዲሰጥዎ እንጠይቃለን።

በእኔ በኩል ለአሜሪካው መሪ ሊገለጹ የሚገባቸው ዋና ዋናዎቹ አራቱ ጉዳዮች እነዚህ ናቸው። በኢኮኖሚ መስክ የሚያስፈልገውን አቶ ይልማ ሊጨምር ይችላል።

ጸ.ት ወልደጊዮርጊስ፣ ግርማዊነትዎ ለፕሬዚዳንት ሩዝቬልት በሚልኩት ማስታወሻ ላይ የሚገልጿቸውን ዋና ዋና ጉዳዮች፣ አቶ አክሊሉ በአራት መንገድ ከፍሎ ያቀረበው በጣም ጥሩ ሆኖ ይታየኛል። ይልቁንም የጉዳዮቹ አቀራረብ በደብዳቤ ሳይሆን <u>በሜሞራንደም መልክ</u> ተዘጋጅቶ ራሱ መልዕክተኛዎ አቶ ይልማ በጃንሆይ ስም ሆኖ ቢያቀርበው ይሻላል የተባለው ሐሳብ የሚደገፍ ነው። እንደሚታወቀው፣ በደብዳቤ መግለጽ የሚቻለው የተወሰነ ጉዳይ ብቻ ነው። በሜሞራንደም (ማስታወሻ) የሆነ እንደሆነ፣ ብዙዎቹን ጉዳዮች በየመልካቸው ተንትኖ ማቅረብ ይቻላል።

ጃንሆይ፣ ወልደጊዮርጊስ እንደተናገርከው አክሊሉ ያጠናው ሐሳብ ማለፊያ ነው። በአሜሪካ ለሚደረገው ጉባኤ ዋና መላክተኛችን አድርገን የምንልከው፣ ከሥራው ጠባይ ጋር የሚዛመድ ስለሆነ፣ <u>ይልማ ዴሬሣ እንዲሆን እኛም ፈቃዳችን ነው።</u> ይልማ አሜሪካ በሚቆይበት ጊዜ ዕድሉ ካጋጠመው፣ ስለ አገራችን ሁኔታ ለፕሬዚዳንቱም ሆነ ለታላላቅ ባለሥልጣኖች የሚያስረዳውን አክሊሉ በአራት መንታ ከፍሎ ከዘረዘራቸው ጉዳዮች ውስጥ፣ <u>እንግሊዞች ስለሚፈጽሙብን በደል</u>

የተባለውን ሙሉ በሙሉ ለመቀበል ተቸግረናል። ሁላችሁም እንደምታውቁት፣ አሜሪካኖችና እንግሊዞች እንደ ወንድማማቾች የሚቆጠሩ ናቸው። ስለዚህ፣ አንደኛው ወንድም ያደረሰብንን በደል ለሌላው ወንድም ስሞታ ማቅረቡ ምን ያህል ሊረዳ ይችላል? ... እስቲ በዚህ በኩል ያደረብንን ጥርጣሬ፣ አክሊሉ በተማርከው በፖለቲካም ሆነ በሕግ የሚመስልህን አስተያየት አቅርብልን። ...

አክሊሉ፣ ጃንሆይ እንዳሉት አብዛኛዎቹ አሜሪካኖችና እንግሊዞች፣ በዘርም ሆነ በቋንቋ በሥልጣኔም ሆነ በሃይማኖት፣ ወንድማማቾች ናቸው። ሆኖም ዛሬ በአለንበት ዘመን በሁለቱ ወንድማማቾች መካከል በሀብትም ሆነ በአቅም አሜሪካኖች እንደታላቅ፣ እንግሊዞች እንደ ታናሽ ሆነው ይታያሉ። በዚህ ረገድ እኛም የተበደልነውን የምንገልጸው ተሰሚነት ላለው ለታላቅ ወንድም ነው። የምናቀርበውም፣ በክስ ወይም በሐሜታ መልክ ሳይሆን፣ በዲፕሎማሲ መንፈስ ታላቅ ታናሹን መክሮ እንዲያግባባን ነው። ግርማዊነትዎ እንደሚያውቀው፣ በአሁኑ ሰዓት የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ከአሜሪካ በስተቀር የማንንም አስተያየት አያዳምጥም። ስለዚህ በእኛ በኩል ብርቱ ጥረት ማድረግ ያለብን፣ የደረሰብንን በደል ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ለመስማት እንዲችል ነው። በእኔ በትንሹ አገልጋይዎ አመለካከት፣ አቶ ይልማ ከግርማዊነትዎ በሚቀበለው "ሚሲዮን" በጣም ደስ የሚያሰኝ ውጤት እንደሚያስገኝ እርግጠኛ ነኝ።

ጃንሆይ፣ አክሊሉ ለጠየቅንህ የሰጠኸው መልስ የሚያረካ ሆኖ አግኝተነዋል። መኰንን ሀብተወልድ! ... በአንተ በኩል የምታቀርበው ሐሳብ ካለ ተናገር! ...

መኰንን ሀ.ወ፣ (ለፈገግታ ያህል) መቸም ሁላችንም እንዳየነው፣ አቶ አክሊሉ የእኔን የእርሻ ሚኒስትሩን ሥራ ለሌላ ሰው እንዲሰጥ አጠንክሮ ባመለከተው መሠረት፣ ጃንሆይ ተስማምተው ወስነዋል። በዚህ ማህል እኔ መጐዳቴ እንዲታወቅልኝ ከማሳሰብ በስተቀር ምን እጨምርበታለሁ? ... ሳቅ ...

ጃንሆይ፣ አየህ መኰንን! አክሊሉ እኮ ድካም ላይ እንዳትወድቅበት አስቦ አዳነህ እንጂ፣ አልጐዳህም። ... እንግዲህ! ወልደጊዮርጊስ በዚሁ ወደን በፈቀድነው መሠረት ይፈጸም! ...

ከዚህ በላይ እንደታየው ንጉሠ ነገሥቱ በወሰኑት መሠረት፣ ይልማ ዴሬሣ ወደ ዋሽንግተን ጉዞአቸውን ከመጀመራቸው በፊት፣ በጽሕፈት ሚኒስትሩ በጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ቢሮ ስለመልዕክቱ ጉዳይ በተደረገው የመጨረሻ ስብሰባ ላይ፣

አቶ መኰንን ሀብተወልድ የእርሻ ሚኒስትር፣

አቶ መኰንን ደስታ የትምህርት ሚኒስትር፣

ብላታ ኤፍሬም ተወልደመድህን የውጭ ጉዳይ ም/ሚኒስትር፣

አቶ ይልማ ዴሬሣ የገንዘብ ም/ሚኒስትር፣

አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ የጽሕፈት ም/ሚኒስትር፣

ተገኝተው ነበር። ለመልዕክተኛው የሚያስፈልገው ዝግጅት በሚገባ የተጠናቀቀ መሆኑ ከተረጋገጠ በኋላ፣ ስብሰባው ከመበተኑ በፊት ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ለአቶ ይልማ ዴሬሣ ሚሲዮን መልካም ምኞት በመግለጽ የሚከተለውን ተናገሩ።

**ክቡር አቶ ይልማ!**

እንደምታውቀው፣ የምንወዳት አገራችን የፋሽስት ቀንበር ተጠምዶባት ለአምስት ዓመታት ከተሠቃየች በኋላ፣ ነፃነታችንን ለማስመለስ የተዋጉልን እንግሊዞች በፋሽስት ቦታ ተተክተው በቅኝ ግዛት ወግ ያስተዳድሩናል። ከዚህ እጅግ አሳዛኝ ከሆነው ሥቃይ ለመገላገል የምንችለው በምን ዘዴ ነው? ብለን ስናጠና፣ ያገኘነው ምርጫ ከሁለት የማይበልጥ ነበር። ይኸውም የመጀመሪያው፣ የታወቀው የኢትዮጵያ ጀግና ራስ አበበ አረጋይ እንደተናገረው፣ ከጠላት ጋር ሲዋጉ ኖረው ትጥቃቸውን ያልፈቱትን አርበኞቻችንን ይዘን ጫካ በመግባት መዋጋትና፣ ብናሸንፍ ነፃነትን፣ ብንሸነፍ ሞትን፣ መቀበል ነው። ሁለተኛው፣ መራራ የሆነውን ትዕግሥት ተመርኩዘን፣ ከባለጋራዎቻችን ጋር በፖለቲካና በዲፕሎማሲ ሜዳ እየታገልን ነፃነታችንን ማስመለስ ነው። ከእነዚህ ከሁለቱ አማራጮች፣ ለጊዜው ሁለተኛው ይሻለናል ብለን ከጀመርነው፣ ይኸው ሁለተኛው ዓመታችን ሆኗል። (1941-1943) ይህንንም እስከ መቼ እንደምንዘልቀው አናውቀውም። አሁን በዚህ የዓለም የእርሻና የምግብ ጉባኤ ምክንያት፣ አቶ ይልማ ወደ ዋሽንግተን ሔዶ፣ ወዳጆቻችን የተባሉት እንግሊዞች በቅኝ ግዛት አስተዳደር አፍነው የሚፈጽሙብንን ግፍ፣ ለአሜሪካ የፖለቲካ መሪዎች እንዲያስረዳና ከተቻለም እርዳታ እንዲያስገኝ ቢሞክር ይሻላል ሲል፣ አብሮ አደግ ወንድምህ አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ ባቀረበው ሐሳብ መሠረት፣ ይኸው የአገርህ የኢትዮጵያና የንጉሠ ነገሥትህ አደራ አንተ ላይ ወድቋል። ይህም ትልቅ አደራ ለአንተ የተሰጠው፣ ያለ ምክንያት አይደለም።

- ንጉሠ ነገሥታችን በወዳጅ አገር እርዳታ ነፃነትን ይዤላችሁ መጣሁ ብለው በናፈቃቸው ሕዝባቸው መካከል ሲገኙ፣ ወዳጅ የተባለው አገር ምን ዓይነት ነፃነት አዘጋጅቶ እንደጠበቃቸው ከአንተ የበለጠ ያስተዋለ የለም።

- እስከዛሬ ድረስ በአገራችን ላይ እንግሊዞች ሥልጣናችንን ነጥቀው የሚፈጽሙብን ግፍ ምንና ምን መሆኑን፣ ከአንተ የበለጠ ዝርዝሩን የሚያውቅ የለም።

- ከፋሺስት ይዞታ ወደ ኮሎኒያሊስት አስተዳደር ለመሻገር የተገደደችውን አገራችንን ወደ ነፃነቷ ለመመለስ፣ ታላቁና ኃያሉ የአሜሪካ መንግሥት በነፍሳችን እንዲደርስልን፣ በምን ቋንቋ ብንነግረው፣ በምን አኳኋን ብናስረዳው፣ እንደሚራራልን ዘዴውንና ጥበቡን ለማግኘት ከአንተ የተሻለ የለም። ስለዚህ፣ ለምንወዳት አገራችን የተቻለህን ሁሉ ከማድረግ እንደማትቆጠብ የሁላችንም እምነት ነው። በምን አኳኋን ዕድላችን እንደሚቃና መንገዱን የምትመርጥ አንተ በመሆንህ፣ ጃንሆይ ከሙሉ ዕምነት ጋር ሙሉ ሥልጣን ሰጥተውሃል። እንግዲህ! ለዚሁ ሁሉ

እግዚአብሔር ይርዳህ እያልኩ መልካም ምኞቴን ከገለጽኩ በኋላ፣ በዕድሜም በአገልግሎትም የሁላችን ታላቅ የሆነው ክቡር አቶ መኰንን ሀብተወልድ የሚያስበውን እንዲናገር በታዬን እለቃለሁ።

መኰንን ሀ.ወ፤ ልጅ ይልማ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ደህና አድርጎ ተናግሮታል። እኔ የምጨምረው ነገር ቢኖር፣ በጣም ትንሽ ነው። የተጣለብህ አደራ ከባድ መሆኑን ሁላችንም እናውቃለን ብለናል። ሆኖም የኃላፊነቱን ክብደት ሳይሸከሙት መገመትና ኃላፊነቱን ተሸክሞ ክብደቱን ማወቅ፣ የተለያየ ነው። ስለዚህ፣ አንተ ላይ የተጣለው አደራ ክብደቱ ምን ያህል እንደሚመዝን የምታውቅ አንተ ብቻ ነህ። እኛ የምናስብልህና የምንመኝልህ፣ ልጅ ይልማ አሜሪካኖችን አግባብቶ፣ ለዚች ለተበደለች አገራችን አጋር ሆነው እንዲደርሱላት በሚያደርገው ጥረት፣ እግዚአብሔር ይርዳው እያልን ነው። መልካም መንገድ ያድርግልህ ...

ይልማ ዴሬሣ፤ ታላላቆቼ ክቡር ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና ክቡር አቶ መኰንን ሀብተወልድ የገለጻችሁልኝ አስተያየት በአዕምሮዬ ስለተቀረጸ፣ ለሥራዬ መልካም ድጋፍ ሆኖ እንደሚረዳኝ እርግጠኛ ነኝ። እዚህ ላላችሁት ለታላላቆቼና ለጓደኞቼ፣ በአጭሩ ለማረጋገጥ የምፈልገው፣ ለእኔ ለይልማ ዴሬሣ በዚህ ዓለም ከኢትዮጵያ የሚበልጥብኝ ነገር የለም። ስለዚህ፣ ለተላኩበት ለአሜሪካ፣ ለሚያዳምጡኝ የአገሬን ችግር በተቻለኝ ዘርዝሬ አስረዳለሁ። ለሚከራከሩኝም በተቻለኝ ጠንክሬ እሟገታለሁ። አንድ ጊዜ ክቡር ጸሐፊ ትዕዛዝ አስተያየት ሲሰጡ፣ "ሥራ ሳይጀመር ብዙ የሚናገር ብዙ አይሠራም" ብለዋል። ስለዚህ እኔም፣ ጥቂት የምናገርና ብዙ የምሠራ ሆኜ ለመገመት እንድችል፣ ንግግሬን ማሳጠር እወዳለሁ። ለሰጣችሁኝ ጥልቀት ላለው ምክርና ለገለጻችሁልኝ የጋለ መልካም ምኞት፣ ከልብ የሆነ ምስጋናዬን እያቀረብኩ፣ በሰላም ይግጠመን ብዬ እሰናበታችኋለሁ።

እንግዲህ፣ ማንም ሰው በቀላሉ እንደሚገነዘበው፣ ኢትዮጵያን ከእንግሊዞች የሞግዚት አስተዳደር ለማላቀቅ፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ እና መንግሥታቸው ቆርጠው የተነሡ ናቸው። በተለይም የንጉሠ ነገሥቱ ሚኒስትሮችም፣ እርስ በርሳቸው የሚያደርጉት ትብብርና መረዳዳት እጅግ የሚያረካና ተስፋ የሚያሳድር ነበር። ለዚህም ለአቶ ይልማ ዴሬሣ በተሰጠው ሚሲዮን ዝግጅት ላይ የታየው ሁኔታ ምስክር ሊሆን ይችላል።

## ይልማ፣ በዋሽንግተን ዲሲ

በዚህ ምዕራፍ መጀመሪያ ላይ፣ የይልማ ዴሬሣ የአሜሪካ ሚሲዮን ግብ ምንና ምን መሆኑ እንደተገለጸው፣ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዋና መልዕክተኛ ዋሽንግተን እንደደረሱ፣ ከኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት የተላከውን ልዩ መልዕክት ለአሜሪካው መሪ ለፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ለማቅረብ ቀጠሮ ጠየቁ። የስቴት ዴፓርትመንት፣ (ማለት የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር) እና የዋይት ሐውስ ቤተመንግሥት ኃላፊዎች ከተወያዩበት በኋላ፣ የተሻለው መንገድ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት እ.ኤ.አ ሐምሌ 7 ቀን 1943 ዓ.ም የዓለም የእርሻና የምግብ ጉባኤ

የመልዕክተኞች መሪዎች የሆኑትን የሬሴፕሽን ግብዣ በማድረግ ስለሚቀበሉ፣ በዚሁ ዕለት ክቡር አቶ ይልማ ዴሬሣ የንጉሠ ነገሥቱን ልዩ መልዕክት ለማቅረብ እንዲችሉ ተወሰነ። በመሠረቱ ይልማ ዴሬሣ የያዙት ዋናው መልዕክት፣ ኢትዮጵያ በእንግሊዞች ወታደራዊ አስተዳደር የደረሰባትን ችግር፣ በተቻለ ያህል ለአሜሪካው መሪ በቃል ለማስረዳትና በሜሞራንደም (ማስታወሻ) ያዘጋጁትንም ጽሑፍ አያይዞ በእጅ ለመስጠት ነው። በተጨማሪም፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ለወዳጃቸው ለፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ፊርመው የላኩትን የመታሰቢያ ፎቶግራፍ ለማቅረብ፣ ይልማ ተዘጋጅተዋል። ነገር ግን የዋይት ሐውስ ፕሮቶኮል ሹም፣ አቶ ይልማ ዴሬሣ ፕሬዚዳንቱን እንዲያነጋግሩ የፈቀደላቸው ጊዜ፣ ከሰባት (7) ደቂቃዎች የማይበልጥ ስለሆነ፣ በዚች ጊዜ ውስጥ የኢትዮጵያን ዋና ዋና ችግሮች አሟልቶ ለማስረዳት፣ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መልዕክተኛ እጅግ የከበደ ነበር። ይሁን እንጂ፣ ከሎንዶን ስኩል ኦፍ ኢኮኖሚክስ (School of Economics) የተመረቁትና ጣዕም ያለው እንግሊዝኛ ተናጋሪ የሆኑት ይልማ ዴሬሣ፣ አቀራረባቸውና የሚገልጹት ሐሳብ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልትን ስለማረከ፣ የፕሮቶኮል ሹሙ የገደበላቸው የሰባት ደቂቃዎች ጊዜ ቢያልፍም፣ የኢትዮጵያ መልዕክተኛ አገራቸው የደረሰባትን በደል ዘርዝረው ለማስረዳት እንዲችሉ በፕሬዚዳንቱ ፈቃድ ጊዜ ተጨመረላቸው።

አቶ ይልማ ዴሬሣ፣ ኢትዮጵያ የነፃነት አጋሮቿ ሆነው የመጡት እንግሊዞች፣ ዘወር ብለው ምን ያህል በደል እንዳደረሱባትና ሕዝቦቿን ለማስተዳደር መብቷን ነፍገው ምን ያህል እንዳስቸገሯት፣ አድማጭን በሚስቡና የርኅራኄን ስሜት በሚቀሰቅሱ ቃላቶች ለአሜሪካው መሪ ካስረዱ በኋላ፣ ንግግራቸውን ሲፈጽሙ፣

" ... ክቡር ፕሬዚዳንት፣ በኢትዮጵያና በታላቁ ገዥዬ በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ስም ሆኜ ያቀረብኳቸውን ሐሳቦች፣ ለዚች ለምታሳዝንና ከባድ ችግር ላይ ለወደቀች አገሬ አንዳንድ እርምጃዎች ለማድረግ እንዲያስችልዎ በማሰብ፣ ልዩ ሜሞራንደም ስለአዘጋጀሁ፣ እንዲቀበሉኝ ከፍ ባለ ትሕትና እለምናለሁ ... " በሚል ቃል ማስታወሻቸውን አቀረቡ።

ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት በጣም ተደሰተ። ይልማ ዴሬሣ የት አገር እንደተማሩና በምን ሙያ እንደተመረቁ ጠይቆ ከተረዳ በኋላ፣ የሚከተለውን ተናገረ። " ... እናንተ ኢትዮጵያውያኖች፣ አገራችሁ ኢትዮጵያ ያላትን የተከበረ ጥንታዊ ታሪክና ባሕል የማንፀባረቅ ተሰጥዎ ያላችሁ ናችሁ። እኔ የዩናይትድ ስቴትስ መሪ ከሆንኩበት ጊዜ ጀምሮ፣ የንጉሠ ነገሥት ኃይለሥላሴን መልዕክተኛ ስቀበል ዛሬ ለሁለተኛ ጊዜ ነው። ዐሥር ዓመት ከሚሆን ጊዜ በፊት፣ የንጉሡ አማች የነበሩትን ራስ ደስታ ዳምጠውን በዋይት ሐውስ ተቀብዬ ሳነጋግር፣ በእኝህ ትልቅ ሰው ላይ ያየሁትን ኢትዮጵያዊ ባሕልና ጨዋነት፣ እርጋታና አስተዋይነት ሁልጊዜ አስታውሳለሁ። ምን ይሆናል? እኝህን የመሰሉ ታላቅ ሰው በክፉዎቹ ፋሽስቶች እጅ በሚያሠቅቅ ሁኔታ መገደላቸውን ዘግይቼ ስሰማ እጅግ አዘንኩ። ይህንንም መሪር ሐዘኔን ለወዳጄ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ጽፌላቸዋለሁ። አንተም፣ ከንጉሠ ነገሥቱ የተላከልኝን መልዕክት ደህና አድርገህ በማስረዳትህ ብቻ ሳይሆን ሐሳቡንም በጽሑፍ ማስታወሻ ስላቀረብክልኝ በጣም አመሰግናለሁ። ከነገርከኝ እንደተረዳሁት፣ አንተ እዚህ በዋሽንግተን በምትቆይበት ጊዜ፣ ሊፈጸሙ የሚችሉትን ጉዳዮች እንድታውቀው ይደረጋል ... " ብለው አሰናበቷቸው።



ክቡር አቶ ይልማ ዴሬሳ

የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት ም/የገንዘብ ሚኒስትር
" ... ሥራ ሳይጀመር ብዙ የሚናገር ብዙ አይሠራም እንደተባለው፤ እኔም ጥቂት የምናገርና ብዙ የምሠራ ሆኜ ለመገኘት እጥራለሁ። ... "

(Y.D June 1943)

# የይልማ ዴሬሣ ሜሞራንደም (ማስታወሻ)*

ክቡርነትዎ እንደሚያውቀው ከዐሥራ ሦስት ዓመታት በፊት በቻይና ላይ ተጀምሮ የዛሬውን ዓለም፣ ዳር እስከ ዳር በማናወጥ በብዙ ሕዝቦች ላይ ከፍተኛ ጉዳት ያስከተለው የወረራ ማዕበል ተጠቂ ከሆኑት ከመጀመሪያዎቹ አገሮች አንዷ ኢትዮጵያ ነች።

አገራችን ከወራሪው ጠላት ነፃ የምትሆንበት ጊዜ እንደተቃረበ፣ ንጉሠ ነገሥቱና መላው የኢትዮጵያ ሕዝብ የወሰዱት እርምጃ፣ አጋሮቻችን ለሆኑት ለታላቋ ብሪታንያ መንግሥትና ሠራዊት የተሟላ ትብብር ማድረግ ነበር። ይህንኑ ፈለግ በመከተል፣ ቀደም ሲል በመላው ዓለም ተበታትነው የነበሩት ኢትዮጵያውያን ስደተኞች ወደ አገራቸው በመመለስ፣ በንጉሠ ነገሥቱ የሚመራውን ነፃ አውጭ ሠራዊት ተቀላቀሉ። በዚያ በአምስቱ ዓመታት የፋሽስት የመከራ ዘመንም፣ ለአገራቸው ነፃነት በብርቱ ሲታገሉ የነበሩት አርበኞቻችን፣ ከጠላት የጦር መሥመር ጀርባ ሆነው የተጠናከረ ውጊያ በማካሔድ፣ ከፍተኛ የሆነውን ተጋድሎ ፈጽመዋል። ዛሬ በወራሪዎች የተያዙት የአውሮፓ አገሮች ሰላማዊ ዜጎች እንደሚያደርጉት ሁሉ፣ የአገራችን ዜጎችም በጠላት ላይ የሽምቅ ውጊያ በማካሄድና የነፃ አውጭዎቹን ሠራዊቶች በመቀላቀል፣ ከፍተኛ ውጤት ያስገኘ ተግባር ፈጽመዋል። በዚህም አኳኋን፣ እያንዳንዱ ኢትዮጵያዊ በጉጉት ሲጠብቀው የነበረውን የአገሩን ነፃነት በተሟላ መልኩ ለማረጋገጥ የሚችለውን ሁሉ አድርጓል። የአገራችን ከአክሲስ ቡድን ነፃ መሆን፣ በእነዚሁ ኃይሎች ወረራ ሥር ለሚገኙና ለነፃነታቸው ለሚታገሉት ሕዝቦች፣ መልካም አርዓያ እንደሚሆን የእያንዳንዱ ኢትዮጵያዊ ዕምነት ነበር። የኢትዮጵያ ነፃነቷን መቀዳጀትና የሕዝቧም የአገሩ ባለቤትነት መረጋገጥ፣ ዛሬ ለነፃነታቸው ለሚታገሉት ለጀግኖቹ ቻይናውያን፣ ቼኮችና ፖላንዶች፣ ኖርዌጂያኖችና ዳኖች፣ እንዲሁም የምሥራቅ ኢንዲስ ተወላጆች፣ ታላቅ የመንፈስ ማነቃቂያ ይሆንላቸዋል። የአትላንቲክ ቻርተር መንፈስ በዚህ አኳኋን በተግባር ላይ መዋል፣ ለሌሎች የተባበሩት መንግሥታት ሕዝቦችም ጠንካራ የህልውና ዋስትናን እንደሚሰጣቸው የታወቀ ነው።

ጠላት ድል ሆኖ አገራችን ነፃ ከሆነች በኋላ፣ በታላቋ ብሪታንያ መንግሥትና በኢትዮጵያ መካከል ስምምነት እስኪፈረም ድረስ፣ አገራችን በጦር ኃይል እንደተያዙት የጠላት የቅኝ ግዛቶች አንዷ ሆና እንደምትቆጠርና፣ በዚሁ መልክ እንደምትተዳደር፣ አጋሮቻችን ሆነው የመጡት የብሪታንያ የጦር መሪዎች ለንጉሠ ነገሥቱ አስታወቋቸው። የዚህም ስምምነት ረቂቅ ለንጉሠ ነገሥቱ ሳይቀርብ ብዙ ወራቶች አለፉ። በእነዚህ ጊዜያቶች ውስጥ፣ ጠላት ሲባረር ትቷቸው የሔደውንና፣ ኢትዮጵያን እንደገና ለማቋቋም እጅግ ጠቃሚዎች የሆኑትን የኢንዱስትሪና የቴክኒክ ዕቃዎችን፣ የመገናኛ አውታሮችን፣ የቴሌፎንና የኤሌክትሪክ አገልግሎት መሣሪያዎችን፣ የታላቋ ብሪታንያ የጦር ኃይሎች እየነቀሉ ወደ ኬንያ ግዛታቸው ሲያሻግሩ ቆዩ። ከዚህ በላይ ደግሞ እጅግ አሳዛኝ የሆነው፣ በትራንስፖርት እቅም ምክንያት ሊወስዱ ያልተቻሉትን ልዩ ልዩ የፋብሪካ ሞተሮች፣ ለአገራችን አገልግሎት እንዳይሰጡ ግማሾቹን በማቃጠል ሌሎቹንም በመሰባበር ከጥቅም ውጭ አደረጓቸው።

* National Archives 884.0077-1443

ከላይ እንደተጠቀሰው፣ በሁለቱ አገሮች መካከል ለሚፈረመው ስምምነት የመጀመሪያው ረቂቅ የቀረበው፣ ኢትዮጵያን በታላቋ ብሪታንያ የሞግዚት አስተዳደር ተይዛ እንድትቆይ የሚያደርግ ነበር። ይህንን ሐሳብ ንጉሠ ነገሥቱ ወዲያውኑ ውድቅ እንዲሆን አደረጉት። ከዚህ በኋላ እንደገና ተዘጋጅቶ የቀረበውና እስከ መጭው ጥር ወር 1944 ዓ.ም ድረስ እንዲሠራበት የተፈረመው ውል፣ የአንድን ነፃ መንግሥት ሉዓላዊነት የሚነካና ከአትላንቲክ ቻርተር መርሖ ጋር ፈጽሞ የማይጣጣም ነው። በውሉ ውስጥ በኢትዮጵያ ላይ የተደረጉት ማዕቀቦችና ገደቦች፣ አገራችን ያለ ፍላጎቷ የተጣለባት ጫና እንደነበረና፣ ስምምነቱም የተፈረመው ከነፃ ፈቃድ ውጭ በግዴታ መሆኑን ለመገንዘብ አያዳግትም።

ይህ እስካሁን የምናከብረው ስምምነት፣ በመጭው ጥር ወር 1944 ዓ.ም ማለት ከስድስት ወራት በኋላ የሚያበቃና በምትኩ አዲስ ስምምነት እንድናደርግ የሚጠበቅ ነው። ስለዚህ፣ የክቡርነትዎ ፈቃድ ሆኖ፣ ወደፊት ከታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ጋር ለመፈራረም የምናዘጋጀውን ስምምነት ለመደራደር የሚያግዘን፣ አንድ ብቁ የሆነ የሕግ ባለሞያ እንዲመደብልንና ውሉም ከአትላንቲክ ቻርተር መንፈስ ጋር እንዲጣጣም በምናደርገው ጥረት፣ የአሜሪካ መንግሥት አስፈላጊውን የዲፕሎማሲ ድጋፍ እንዲሰጠን፣ ክፍ ያሉት ገዥዎ ንጉሠ ነገሥት ኃይለሥላሴ ለክቡርነትዎ በስማቸው እንዳመለክት አዘውኛል።

## የባሕር በር ጉዳይ፤

የነፃነት አፍቃሪዎች የሆንን ሕዝቦች፣ በብርቱ ትግል ለምንገነባው ለነገው ዓላማችን፣ አስፈላጊዎች ናቸው ከሚባሉት ቅድመ ሁኔታዎች አንዱ፣ ነፃ የሆነ የሀብት ዝውውር የሚከናወንበትን የባሕር በር መመሥረት ነው። አንድ አገር ሊያድግና ሊበለጽግ የሚችለው፣ በልዩ ልዩ መስክ የሚያመርታቸውን ወደ ውጭው ዓለም ለመላክ ሲችልና፣ በአንፃሩም ከውጭ የሚያስፈልጉትን ዕቃዎችና የጤና መከላከያዎች በነፃነት ወደ አገሩ ለማስገባት ሲችል ነው። አራት መቶ ሀያ ሦስት ሺህ ዘጠኝ መቶ ሁለት ስኩዌር ማይልስ የቆዳ ስፋት ያላትና፣ ከሰፊ የተፈጥሮ ሀብት ጋር የአሥራ አራት ሚሊዮን ሕዝብ ነዋሪ የሆነችው ኢትዮጵያ፣ ከቅርብ ዓመታት ወዲህ የባሕር በር ተነፍጋት ትኖራለች። ይህም ሁኔታ በአገራችን ዕድገት ላይ ምን ያህል ደንቃራ ሆኖ እንደዘጋብን መገመት ይቻላል። በተጨማሪም የባሰ ይባስ ተብሎ፣ በኢትዮጵያ ዙሪያ ቅኝ ግዛቶቻቸውን አስፋፍተው የባሕር በሮቻችንን በሙሉ የያዙት የአውሮፓ አገሮች፣ እርስ በርሳቸው ተነጋግረው የጦር መሣሪያዎች ወደ አገራችን እንዳይገቡ በ1884 ዓ.ም የስምምነት ውል ተፈራረሙ። በዚህም መሠረት፣ በ1935 ዓ.ም ኢትዮጵያ የጠላት ወረራ በደረሰባት ጊዜ፣ ከአውሮፓ አገሮች በገንዘቧ የገዛቻቸውን የጦር መሣሪያዎች እንኳ እንዳታገኝ በሩን ስለዘጉባት፣ የመጣባትን ጠላት በመሣሪያዎች እጦት ምክንያት ለመመከት ሳትችል ቀረች።

ዛሬ "ኤርትራ" በሚል ስም የሚጠራው አገር፣ ከኮሎኒያሊስት ይዞታ በፊት "ሐማሴን" የሚባልና ከኢትዮጵያ ክፍለ ሀገሮች አንዱ የሆነ፣ ሕዝቡም ከኢትዮጵያ ሕዝብ ጋር በዘርና በባሕል፣ በሃይማኖትና በቋንቋ ተዋህዶ የሚኖር ነበር። ይህንን መሠረታዊ ታሪክ በትክክል የሚያውቁት ወዳጆቻችን እንግሊዞች፣ ፋሽስትን ከኤርትራ ቅኝ ግዛቱ ለማባረር በ1940 ዓ.ም ከሱዳን ድንበር ተነሥተው ውጊያውን ሲጀምሩ፣ የኤርትራ ሕዝብ በገዥዎቹ በጣልያኖች ላይ ዐመፅ ካነሣ እና ከተባበረ፣ ከኢትዮጵያ ጋር የመቀላቀል ዕድሉን እንደሚሰጡት ቃል ገብተውለት ነበር።

የኤርትራም ሕዝብ በተሰጠው ቃል መሠረት፤ ግዳጁን ፈጽሟል። አሁንም ቀደም ብዬ እንደጠቀስኩት፤ በኮሎኒያሊስት ኃይል ያለውዴታቸው ተለያይተው የኖሩት እነዚህ የኤርትራና የኢትዮጵያ ሕዝቦች እንዲዋሐዱ ለምናደርገው ጥረት፤ የክቡርነትዎ ድጋፍ እንደማይለያቸው፤ ንጉሠ ነገሥት ኃይለሥላሴ ጽኑ ተስፋ ያደርጋሉ።

ኢትዮጵያ ለሰባት ዓመታት ባሳለፈችው የመከራና የጦርነት ዘመን ከፍተኛ ጉዳት የደረሰባት ስለሆነ፤ ተመልሶ ለመቋቋም እንድትችል የገንዘብና የማቴሪያል እርዳታ ያስፈልጋታል። ከፍተኛ የገንዘብ እጥረት ስለደረሰባትም፤ በአሁኑ ጊዜ የአንድን አገር መንግሥት ለማካሔድ የሚያስፈልጉትን መሠረታዊ ጉዳዮች ማግኘት አልቻለችም። ከዚህ ብርቱ ችግር ለመላቀቅ፤ የሚያስፈልገውን የገንዘብ ብድርና የልዩ ልዩ ማቴሪያል እርዳታ በአፋጣኝ ለማግኘት እንድትችል፤ ክቡርነትዎ ለአስተዳደር ኃላፊዎችዎ የድጋፍ ሐሳብ እንደሚሰጡልን ግርማዊ ንጉሠ ነገሥት ተስፋ አድርገዋል።

አሜሪካውያን ባለሞያዎች፤ በፋይናንስ፣ በፍትሕና በአስተዳደር፤ እንዲሁም በሌሎች ቴክኒካዊ ጉዳዮችና የጦር ሠራዊት በማቋቋም፤ ለኢትዮጵያ የሚያበረክቱትን ድጋፍና የሚሰጡትን ምክር፤ ንጉሠ ነገሥት ኃይለሥላሴ በደስታ ይቀበላሉ። እንዲሁም የአሜሪካ የካፒታልና የቴክኒክ ድጋፍ፤ የአገራችንን የተፈጥሮ ሀብት በማልማት ረገድ የሚኖረውን አስተዋጽኦ፤ ንጉሠ ነገሥቱ በሚገባ ተረድተውታል። የአሁኑ የዓለም ጦርነት ተፈጽሞ የመልሶ ግንባታ እንቅስቃሴ ሲጀመር፤ የምግብ ዝግጅቶችን ወደሚፈለጉባቸው ወደ አውሮፓና ወደ ምሥራቅ አገሮች በመላክ ረገድ፤ ኢትዮጵያ የሚኖራትን ሚና ንጉሠ ነገሥቱ ገና ከወዲሁ ተገንዝበውታል። አስፈላጊው የቴክኒክና የማቴሪያል እርዳታ ከተገኘ፤ እጅግ ተስማሚ የሆነ አየርና ለም አፈር ያላቸው የኢትዮጵያ ደጋማ አካባቢዎች፤ ለእርሻ ልማትና ለከብት እርባታ አመችዎች ናቸው። ከዚህ በተጨማሪም፤ የአሜሪካ ሕዝብ በጦርነት የደቀቀውን የዓለም ክፍል መልሶ ለመገንባት በሚያደርገው አስደናቂ ጥረት፤ የኢትዮጵያ ሕዝብም በሚችለው ሁሉ ከጐኑ ለመሰለፍ ብርቱ ጉጉት እንዳለው መግለጽ እወዳለሁ።

ክቡር ፕሬዚዳንት !

ንጉሠ ነገሥት ኃይለሥላሴ በስደት ላይ በነበሩበት ዘመን፤ እንግሊዞች ያደረጉላቸውን የኢትዮጵያ ሕዝብ አይዘነጋውም። አሁን ግን፤ የኢትዮጵያ ሕዝብ የማናቸውም ነፃ ሕዝብ መብት የሆነውን፤ የራሱን ዕድል በራሱ የመወሰን መብቱ እንዲከበርለት በመታገል ላይ ይገኛል። ይህን መብቱን በተሟላ መልኩ ተግባራዊ ለማድረግ እንዲችል፤ የኢትዮጵያ ሕዝብ የዴሞክራሲ ትልቅ ምሳሌ የሆነችውን የአሜሪካንን ድጋፍ አጥብቆ ይጠይቃል። ይህን የአገራቸውን የወደፊት ሁኔታ በተመለከተ፤ ለክቡርነትዎ አመች በሆነ ጊዜ መጥተው ለመነጋገር ግርማዊ ንጉሠ ነገሥት ልባዊ ፍላጐታቸው መሆኑን በታላቅ አክብሮት እንድገልጽላቸው አዘውኛል።

ፊርማ ይልማ ዴሬሳ
የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት መንግሥት
ም/የገንዘብ ሚኒስትር

# ፍሬያማ ሚሲዮን

ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ከይልማ ዴሬሣ የቀረበለትን ሜሞራንደም አንብቦ በጣም ስለተነካ፣ ወዲያውኑ ለውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ለሚስተር ኮርደል ሁል (Cordel Hull) ማስታወሻውን አያይዞ በላከለት አጭር መምሪያ፣ " ... ይህ ጉዳይ እጅግ የሚያጓጓ ሆኖ ታይቶኛል። እስቲ ስለ ይዘቱ አነጋግረኝ ... " ሲል ጠየቀው።

የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ በሁለት ሳምንታት ጊዜ ውስጥ የበኩሉን ጥናት ካደረገ በኋላ፣ በይልማ ዴሬሣ ማሞራንደም ላይ ያለውን አስተያየት ለፕሬዚዳንቱ አቀረበ።

1. የኢትዮጵያ መንግሥት የገንዘብ ሚኒስትር፣ እንግሊዞች በኢትዮጵያ ላይ ስለሚፈጽሙት በደል በዝርዝር የገለጸቸው ጉዳዮች ሁሉ፣ እውነትና ትክክለኛ መሆናቸውን የደረሱን መረጃዎች አረጋግጠዋል።

2. የታላቋ ብሪታንያ የጦር ኃይል በሚያዝያ 1941 ዓ.ም ፋሽስትን አባርሮ አዲስ አበባን ከያዘበት ዕለት ጀምሮ፣ ኢትዮጵያን ከጠላት ከተወሰዱት ቅኝ ግዛቶች መካከል አንዷ እንደሆነች በመቁጠር፣ በወታደራዊ አስተዳደር እንድትመራ አድርጓታል።

3. ንጉሠ ነገሥቱ በግንቦት ወር 1941 ዓ.ም ወደ አገራቸው እንዲመለሱ ቢደረግም፣ ከታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ጋር የሚያደርጉት ውል እስከተፈረመበት ጊዜ ድረስ፣ ለዘጠኝ ወራት ከማናቸውም ሥልጣን ታግደው፣ አገሪቱ የምትመራው በእንግሊዞች የጠበቀ አገዛዝ ብቻ እንደነበረ ታውቋል።

   ይልማ ዴሬሣ በሜሞራንደሙ እንደገለጸው፣ ንጉሠ ነገሥቱ እንዲፈርሙት መጀመሪያ ተዘጋጅቶ የቀረበላቸው ውል፣ ታላቋ ብሪታንያ ኢትዮጵያን በሞግዚት አስተዳደር ይዛ እንድታቆያት የሚያደርግ ነበር። ይህንን ንጉሠ ነገሥቱ ውድቅ ስለአደረጉትና እምቢታቸውንም ስለአጠነከሩ፣ የኢትዮጵያን ነፃ መንግሥት ተብሎ መጠራትና የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ወደ ዙፋን መመለስ፣ ታላቋ ብሪታንያ ማወቋን የሚገልጽ አንቀጽ በውሉ ውስጥ ተጨምሮበት፣ በጥር 31 ቀን 1942 ዓ.ም ለመፈረም በቅቷል። ይሁን እንጂ፣ የአገሪቱ ጠቅላላ አስተዳደር የሚካሔደው በእንግሊዞች የጦር መኰንኖች ሙሉ ሥልጣን ነው። እነሱ ሳይጠየቁና ሳይፈቅዱ፣ በኢትዮጵያውያን ሥልጣን የሚፈጸም ጉዳይ የለም።

4. ኢትዮጵያ ከታላቋ ብሪታንያ ጋር ያደረገችው ስምምነት፣ ከስድስት ወራት በኋላ በመጭው ጥር 31 ቀን 1944 ዓ.ም ስለሚፈጸም፣ ለሚቀጥለው ውል ዝግጅት ይልማ ዴሬሣ ባቀረባቸው ጥያቄዎች ውስጥ፣

   ሀ/ በኢትዮጵያ በኩል ለሚደረገው ድርድር፣ አንድ የሕግ ባለሞያ የሆነ አሜሪካዊ ለመቅጠር እንዲፈለግለት፣

---

* National Archives 884-014/7-2043

ለ/ የሚዘጋጀው ውል ከአትላንቲክ ቻርተርና ከዩናይትድ ኔሽን ዴክላሬሽን መንፈስ ጋር እንዲጣጣም፤ በኢትዮጵያ በኩል ለሚደረገው ጥረት፤ የአሜሪካ ዲፕሎማሲ እርዳታውን እንዲለግስን እንጠይቃለን ሲል አሳስቧል።

በመሠረቱ እነዚህ ሁለት ጉዳዮች በስቴት ዴፓርትመንት በኩል የሚደገፉ ናቸው። በተለይም ከጥቂት ወራት በኋላ ኢትዮጵያ ከታላቋ ብሪታንያ ጋር የምታደርገው ውል የአገሪቱን ሕልውና የሚጠብቅ እንዲሆን፤ ወዳጆቻችን እንግሊዞችን ማሳሰብና ማስፈጸም ይገባናል። ይልማ ዴሬሣ በጠየቀው መሠረት፤ ሚስተር ጆን ስፔንሰር (John Spencer) የተባለ የሕግ ባለሞያ ተገኝቶ፤ ለውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር አማካሪ እንዲሆን ስምምነት ተደርጓል። ሚስተር ስፔንሰር ከጦርነቱ በፊት ለኢትዮጵያ የሕግ አማካሪ ሆኖ ለጥቂት ጊዜ የሠራ ስለነበር፤ አሁንም እሱ በመገኘቱ የገንዘብ ሚኒስትሩ ተደስቷል።

5. ይልማ ዴሬሣ ከትሬዥሪ ዴፓርትመንት ጋር ሲነጋገር፤ በመጭው ስድስት ወራት ውስጥ ከእንግሊዞች ጋር በሚደረገው ውል፤ የኢትዮጵያ መንግሥት ሙሉ ነፃነት ከተረጋገጠ በኋላ፤ ለኢትዮጵያ የልማት ፕሮግራም እስከ ሃምሣ ሚሊዮን የአሜሪካን ዶላር የሚደርስ ብድር ማግኘት ያስፈልጋል ብሏል። የገንዘብ ሚኒስትሩ የጠየቀውን ሁሉ መፈጸም አስቸጋሪነቱ የታወቀ ቢሆንም፤ ወደፊት እንደሚያቀርበው ዝርዝር የልማት ፕሮግራም እየታየ የተቻለው ሁሉ እንደሚደረግ ተነግሮት ተስማምቷል።

6. ኢትዮጵያ የራሷ የሆነውን ገንዘብ (Currency) ለማተም እንድትችል፤ በአምስት ዓመት ጊዜ ውስጥ የሚከፈል አንድ ሚሊዮን አምስት መቶ ሺህ የሚመዝን የብር ወቄት ብድር ለማግኘት በመቻሉ፤ ይልማ ዴሬሣ ተደስቷል። ካለፉት ሁለት ዓመታት ጀምሮ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ባለሥልጣኖች፤ ኢትዮጵያ በኢስት አፍሪካ ሽልንግ እንድትገበያይ አስገድደው ነበር። ነገር ግን ሕዝቡ በተለይም ገበሬው በጥንቱ በማሪያ ቴሬዛ ብር ሲገበያይ የኖረ ስለሆነ፤ የእንግሊዞችን የምሥራቅ አፍሪካ ሽልንግ አንቀበልም በማለት፤ ምርቱን ለገበያ ባለማቅረቡ ከፍ ያለ ችግር ተፈጥሯል። አሁን ግን ሕዝቡ የንጉሠ ነገሥቱ ምስል ያለበት ገንዘብ ታትሞ ሲቀርብለት ደስታው ከፍ ያለ እንደሚሆንና ችግሩ እንደሚወገድ ይልማ ዴሬሣ እርግጠኛ ነው። በተጨማሪ የገንዘብ ሚኒስትሩ በጠየቀው መሠረት፤ ለኢትዮጵያ ባንክ ገዥ የሚሆን ሰው ተፈልጐ ሚስተር ጆርጅ ብላወርስ (George Blowers) የተባለ አሜሪካዊ፤ ከዚህ ቀደም የላይቤሪያ ባንክ ገዥ የነበረ፤ አሁን በዚሁ ዓይነት ሥራ ወደ አዲስ አበባ ለመሔድ ስለተስማማ፤ ይልማ የሚፈልገውን አግኝቷል።

7. ኢትዮጵያ በሌንድ ሊዝ (Lend Lease) ፕሮግራም ተጠቃሚ እንድትሆን ከዋይት ሐውስ በተፈቀደው መሠረት፤ ይልማ ዴሬሣ አስፈላጊዎቹን ግዴታዎች ለመፈጸም በኢትዮጵያ መንግሥት ስም ሆኖ ስምምነቱን ፈርሟል።

8. በዩናይትድ ስቴትስና በኢትዮጵያ መካከል የነበረው የዲፕሎማቲክ ግንኙነት የተቋረጠው በፋሽስት ይዞታ ምክንያት ስለነበረ፤ አሁን በተቻለ ፍጥነት

የአሜሪካ ለጋሲዮን አዲስ አበባ እንዲከፈት፣ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ደጋግመው መጠየቃቸው ይታወሳል። የገንዘብ ሚኒስትሩ ይልማ ዴሬሣ እንደነገረኝ፣ ንጉሠ ነገሥቱ በአሁኑ ሰዓት ም/የውጭ ጉዳይ ሚኒስትራቸው ሆኖ የሚሠራውን ብላታ ኤፍሬም ተወልደ መድህን የተባለውን በትውልድ ኤርትራዊ የሆነ ኢትዮጵያዊ፣ በአሜሪካ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር አድርገው ለመላክ ወስነዋል። ኤፍሬም በቤይሩት ዩኒቨርሲቲ የተማረና፣ ከጦርነቱ በፊት በፓሪስና በሎንዶን የኢትዮጵያ ዲፕሎማት ሆኖ የሠራ ነው። ንጉሠ ነገሥቱ በስደት እንግሊዝ አገር በኖሩበት ዘመን፣ ኤፍሬም ከረዳቶቻቸው አንዱ ሆኖ አገልግሎቱን ያላቋረጠ ጨዋ ኢትዮጵያዊ ነው ተብሎ ይነገርለታል። ስለዚህም፣ የአግሪመንቱ ጥያቄ እንደቀረበልን፣ በአግባቡ በቶሎ እንዲፈጸም እናደርጋለን። **በዩናይትድ ስቴትስ በኩል በኢትዮጵያ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር እንዲሆን በፕሬዚዳንቱ የተሾመው ሚስተር ጆን ኬኔት ካልድዌል (John K. Caldwell) በቅርብ ጊዜ ውስጥ ወደ አዲስ አበባ ሔዶ አዲሱ ሥራውን ይጀምራል።**

9. የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ዋሽንግተን መጥተው ፕሬዚዳንት ሩዝቬልትን ለማግኘት ያላቸውን ፍላጐት ይልማ ዴሬሣ በሜሞራንደሙ እንደጠቀሰው ሁሉ፣ ለእኔም አንሥቶብኛል። እኔም በሰጠሁት መልስ፣ የአክሲስ አገሮች የመጀመሪያዋ ተጠቂና የመጀመሪያዋ ነጻ ወጭ የሆነችውን የኢትዮጵያን መሪ፣ ፕሬዚዳንታችን የሚቀበሏቸው በደስታ ነው። ሆኖም አሁን በአለንበት የጦርነት ዘመን፣ የታሰበውን ለመፈጸም የሚያመቸው ጊዜ መቼ እንደሚሆን ፕላን ማድረግ ያዳግተናል። ሐሳቡ የሚደገፍና መደረግም ያለበት ስለሆነ፣ ወደፊት ተነጋግረን እንወስናለን ብየው፣ የኢትዮጵያ የገንዘብ ሚኒስትር መስማማቱን ነግሮኛል።

ከዚህ በላይ እንደቀረበው፣ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ሚስተር ሁል ለፕሬዚዳንት ሩዝቬልት በላከው ማስታወሻ ላይ፣ በዘጠኝ ነጥቦች ዘርዝሮ የገለጻቸው ጉዳዮች፣ የአቶ ይልማ ዴሬሣ የአሜሪካ ሚሲዮን እጅግ በሚያረካና በተሟላ መልክ መፈጸሙን ያረጋግጣል። ክቡር አቶ ይልማ፣ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልትን በማነጋገርና ያዘጋጁትንም ሜሞራንደም በእጅ በማቅረባቸው ብቻ ሳይሆን፣ ለውጭ ጉዳይና ለገንዘብ ሚኒስትሮቹ፣ እንዲሁም ለአንዳንድ ለታወቁ የኮንግሬስ አባሎች የኢትዮጵያን ችግር ተንትነው በማስረዳታቸው፣ አሜሪካኖች በዚች አገር ላይ የደረሱትን አሳዛኝ ሁኔታዎች ለመከታተልና በተቻለም ለመርዳት ከፍ ያለ ስሜት አሳድሮባቸዋል።

ይህ መልካም አስተያየት እየቀጠለ እንዲሔድና ልዩ ልዩ እርዳታዎችን ለማስገኘት፣ እንግሊዞችም በኢትዮጵያ ላይ አለአግባብ የሚፈጽሙትን በደል ለመታዘብ፣ ተቋርጦ የነበረው የሁለቱ አገሮች የዲፕሎማቲክ ግንኙነት በቶሎ እንዲቀጥል መደረጉ፣ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት ወሰን የሌለው የደስታ ስሜት ፈጥሯል። የይልማ ሚሲዮን በተከናወነ በጥቂት ሳምንታት ውስጥ፣ በኢትዮጵያ የአሜሪካ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ሆኖ የተሾመው ሚስተር ጆን ኬኔት ካልድዌል አዲስ አበባ ደርሶ ሥራውን ሲጀምር፣ በታሪክ ለመጀመሪያ ጊዜ አዲስ ለተከፈተው የኢትዮጵያ ለጋሲዮን ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር የሆኑት ብላታ ኤፍሬም ተወልደመድህን የሹመት ደብዳቤያቸውን ለማቅረብ ዋሽንግተን ገቡ።

እንደሚታወቀው የጃንሆይ የገንዘብ ሚኒስትር ወደ አሜሪካ የሔዱት፣ በዓለም የእርሻና የምግብ ጉዳይ ጉባኤ ላይ ኢትዮጵያን ለመወከል ስለሆነ፣ አዲስ አበባ ያሉት ኮሎኒያሊስቶቹ እንግሊዞች፣ ይልማ ዴሬሣ እንኳንስ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልትን በሰፊው ለማነጋገር፣ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩንም ቢሆን ለማግኘት ዕድል ይኖራቸዋል ብለው አላሰቡም። የአሜሪካ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር የጃንሆይ መልዕክተኛ ሚሲዮናቸውን ፈጽመው ወደ አዲስ አበባ ከመመለሳቸው በፊት፣ በዋሽንግተን በቆዩበት ጊዜያት ውስጥ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ተቀብለው ማነጋገራቸውንና የተፈጸሙላቸውንም ጉዳዮች በመዘርዘር፣ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት እንዲያውቀው ስለአደረገ፣ አዲስ አበባ ኢትዮጵያን በሚያስቸግሩት የእንግሊዞች የጦር ባለሥልጣኖች ላይ የደረሰው ብስጭት በቀላሉ የሚገመት አልነበረም።

አቶ ይልማ አዲስ አበባ እንደደረሱ፣ ለኢትዮጵያ አስተዳደር ኃላፊ የሆነው፣ የታወቀው ዕብሪተኛ ብሪጋድየር ሞሪስ ለሽ፣ ከታላቋ ብሪታንያ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ከሚስተር ሮበርት ሐው (Robert Howe) ጋር ሆኖ ሊያነጋግራቸው ስለፈለገ፣ በእንግሊዝ ለጋሲዮን ለመገናኘት ቀጠሮ ተደረገ። አቶ ይልማ እንግሊዝ ለጋሲዮን የሔዱት፣ ከገንዘብ ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ከአቶ ምናሴ ለማ ጋር ስለነበረ፣ ከባለሥልጣኖቹ ጋር የተደረገው ውይይት እንዴት እንደነበረ፣ በዋሽንግተን እ.ኤ.አ ጥቅምት 16 ቀን 1994 ዓ.ም አቶ ምናሴ ለዚህ መጽሐፍ ደራሲ የሚከተለውን አጫወቱት።

" ... አቶ ይልማና እኔ እንግሊዝ ለጋሲዮን ስንደርስ፣ የባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትሩ የሚስተር ሮበርት ሀው ሰላምታ አሰጣጥና አቀባበል ጨዋ በሆነ መልክ ነበር። ብሪጋድየር ለሽ ግን በተለመደው ጥጋቡ፣ ከተቀመጠበት ወንበር ላይ ብዙ ሳይነቃነቅ፣ ይልማን ሰላምታ ለመስጠት እጁን ዘረጋለት። ይልማለተዘረጋለት የእጅ ሰላምታ ሳይሰጥ እንደ አሜሪካኖች ሀይ! ብሎት ሚኒስትሩ በሰጠው ወንበር ቁጭ አለ። እኔም ይልማን ተከትዬ አጠገቡ ያለውን ወንበር ላይ ያዝኩ። ወዲያው ሚስተር ሀው፣ ለአቶ ይልማ ጥያቄ አቀረበ። " ... እኛ የምናውቀው ወደ ዋሽንግተን የሔድከው በዓለም የእርሻና የምግብ ጉባኤ ላይ ለመካፈል ነው። ነገር ግን አሁን እንደሰማነው፣ ከአሜሪካ መንግሥት ጋር በንጉሠ ነገሥቱ ስም ሆነህ ልዩ ልዩ ስምምነቶች አድርገሃል። ለሥራችን እንዲረዳን ዝርዝሩን ልትነግረን ትችላለህ? ... " ብሎ ጠየቀ። ይልማ በጣም በረጋ መንፈስ መልሱን ሰጠ። " ... እኔ ዋሽንግተን በቆየሁበት ጊዜ ውስጥ፣ ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት፣ ከሴክሬታሪ ሁል እና ከትሬዥሪው ሴክሬታሪ እንዲሁም ከታላላቅ የኮንግሬስ አባሎች ጋር ተነጋግሬ፣ ለአገሬ ጉዳይ የተፈጸሙልኝንና ያደረግኳቸውን ስምምነቶች ሁሉ በመጀመሪያ ሪፖርት ማድረግ ያለብኝ፣ ለኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት መንግሥት ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ነው እንጂ፣ ለወዳጃችን ለታላቋ ብሪታንያ መንግሥት የዲፕሎማቲክ ሚሽን አይደለም። ሆኖም ንጉሠ ነገሥቱ የማቀርብላቸውን ሪፖርት ካጸደቁትና ከተስማሙበት በኋላ፣ አንተ እንዳልከው ለጋራ ሥራችን ጠቃሚ ይሆናል የምንላቸውን ሁሉ ልንነጋገርባቸው እንችላለን ... " አለው። ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትሩ ሚስተር ሀው፣ ይልማ በሰጠው መልስ መስማማቱን ሲገልጽ፣ ብሪጋድየር ለሽ ጣልቃ ገብቶ፣ " ... እኔ በቶሎ መልሱን ማግኘት ያለብኝ አንድ ጥያቄ አለኝ። በጥር 31 ቀን 1942 ዓ.ም በተደረገው ስምምነት መሠረት፣ እኛ ሳንስማማበትና ሳናውቀው የኢትዮጵያ መንግሥት የውጭ አገር ዜጎች የሆኑ አማካሪዎች መቅጠር አይችልም። ይህንን ባለማወቅ ይሆን አንድ የውጭ ጉዳይ የሕግ አማካሪና የባንክ ገዥ የቀጠርከው? ... " ብሎ ጠየቀ። ይልማ አሁንም በረጋ

መንፈስ መልሱን ሰጠ። " ... መጀመሪያ እኔ በአገሮቻችን መካከል የተፈረመውን ውል በሚገባ አውቃለሁ። ምናልባት ከአጠያየቅህ እንደተረዳሁት፤ የውሉን ትክክለኛ መንፈስ ያልተረዳኸው አንተ ትመስለኛለህ። በስምምነታችን ውስጥ የተጠቀሰው፤ የኢትዮጵያ መንግሥት የውጭ አገር ዜጎች የሆኑ አማካሪዎች ሲቀጥር፤ ለወታደራዊው አስተዳደር ያስታውቃል የሚል ነው እንጂ፤ ያስፈቅዳል የሚል አይደለም። በዚሁ መሠረት፤ በአሜሪካን በቆየሁበት ጊዜ፤ በስቴትስ ዴፓርትመንት ኃላፊዎችና በተለይም የሚስተር ሁልን እርዳታ አግኝቼ፤ የቀጠርኳቸውን አንድ የኢንተርናሽናል ሕግ አማካሪና የባንክ ገዥ፤ እነ ማን መሆናቸውን በቅርብ ጊዜ ውስጥ አስታውቃችኋለሁ። ከዚህ ጋር አያይዤ፤ ለብሪጋድየር ለሽ ማስረዳት የምፈልገው፤ ኢትዮጵያ የታላቋ ብሪታንያ ፍጹም ወዳጅዋ የሆነች ነጻ መንግሥት ነች እንጂ፤ ኰሎኒዋ አይደለችም። ነገር ግን፤ የወታደራዊው አስተዳደር ባለሥልጣኖች የሚያሳዩን ሁኔታና የሚፈጽሙብን ሁሉ የነጻ መንግሥትነታችንን መብት በግልጽ የሚነካ ነው። ይህ ጉዳይ በጣም እያስመረረን ስለመጣ፤ ንጉሠ ነገሥታችን በመጀመሪያ ለጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችልና ለካቢኔያቸው፤ ከዚያም ለነጻዎቹ የዓለም መንግሥታት ማሳሰብ ይገደዱ ይሆናል ... " በማለት አቶ ይልማ በጠነከረ ቋንቋ ተናገረ። በዚህ ጊዜ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትሩ፤ " ... እኔ የሚስተር ቸርችልን መንግሥት የተወከልኩ ዲፕሎማት ስለሆንኩ፤ የደረሰባችሁ ችግር ካለ ተነጋግረን ልናስወግደው እንችላለን ... " ሲል፤ ብሪጋድየር ለሽ ደግሞ፤ " ... እኛ እኮ ከጠላት ጋር ተዋግተንና አሸንፈን ነው የአገራችሁን ነጻነት ያስመለስነው። አሁንም አስተዳደሩን የያዝንላችሁ፤ ከሽፍቶችና ከቀማኞች ለማዳንና የሕዝባችሁን ደኅንነት ለመጠበቅ ነው ... " አለ። ይልማ ወዲያውኑ ቀጠለና፤ " ... እኛም እኮ ደግመን ደጋግመን ተናግረናል። ነጻነታችንን ለማስመለስ የተደረገልንን የታላቋ ብሪታንያን ውለታ ንጉሠ ነገሥቱና የኢትዮጵያ ሕዝብ መቸውንም አይረሱትም። ይህም ሲሆን፤ ጠላትን ለማባረርና ነጻነታችንን ለማስመለስ በተደረገው ጦርነት ከታላቋ ብሪታንያ ጦር ጋር የኢትዮጵያን አርበኞች ተሳትፎና ተጋድሎ እናንተም መዘንጋት የለባችሁም። የእኛ ቅሬታ የመንግሥታችንን ሥልጣን ይዛችሁ የምትፈጽሙብን በደል ስለበዛብን ነው ... " ካለ በኋላ፤ ይልማ ከወንበሩ ብድግ ብሎ ለመሔድ ሲነሣ፤ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትሩ ከቢሮው በር መውጫ ድረስ ሸኘው። ብሪጋድየር ለሽ ግን ከመቀመጫው አልተነቃነቀም። ይልማም ዘወር ብሎ ሰላምታ ሳይሰጠው ሔደ። አቶ ምናሴ እንደነገሩኝ፤ " ... ብሪጋድየር ለሽ ብዙዎቹን የጃንሆይ ሚኒስትሮችን በተለይም የተማሩትን ወጣቶች እንደማይወድ የታወቀ ቢሆንም፤ በተለይ አቶ ይልማን በጣም ይጠላ ነበር። ለምሳሌ፤ አሁን እንዳልኩህ ከእንግሊዝ ለጋሲዮን ስብሰባችን በኋላ፤ አቶ ይልማ አሜሪካ ሆኖ የቀጠራቸውን ለውጭ ጉዳይ አማካሪ ሚስተር ስፔንሰርንና ለባንክ ገዥ ሚስተር ብላወርን፤ የይለፍ ወረቀት ለመስጠት ብሪጋድየር ለሽ ለሁለት ወራት ያህል አጉላላቸው። መቸም የጃንሆይ መንግሥት ከእንግሊዞች ችግር የተላቀቀው የመጀመሪያው የውል ዘመን አልቆ ብሪጋድየር ለሽ ከአዲስ አበባ ተነቅሎ ሲሔድ ነው ... "

ክቡር አቶ ይልማ በዋሽንግተን እነዚያን ሁሉ ታላላቅ ጉዳዮች ፈጽመው አዲስ አበባ ሲመለሱ፤ በጃንሆይና በሚኒስትሮቹ በኩል ምን ዓይነት አቀባበል እንደጠበቃቸው አቶ ምናሴ ለማን ጠይቄያቸው የሰጡኝ መልስ የሚከተለው ነው።

" ... ትክክለኛውን ቀንና ሰዓት ባላስታውስም አቶ ይልማ አዲስ አበባ እንደገባ፤ ከአውሮፕላን ማረፊያ በቀጥታ ገነተ ልዑል ቤተመንግሥት ሔዶ ጃንሆይን አግኝቶ ስለሚሸኑ አስረድቷል። በማግሥቱ በጃንሆይ ቢሮ ንጉሣዊ

ቤተሰቦች አልጋወራሽና ራስ ካሣ፣ ሚኒስትሮች በሙሉ በተሰበሰቡበት ይልማ ሪፖርቱን በዝርዝር አቅርቦ ሲጨርስ፣ ከጃንሆይ ጀምሮ ሁሉም አድንቀው እንደአመሰገኑት ሁላችንም ሰምተናል፡፡ በዚያን ጊዜ የእኔ ደረጃ ዋና ዲሬክተር ስለሆነ፣ ለስብሰባው አልተጠራሁም፡፡ ይልቅ በተለይ እንደሰማነው፣ በስብሰባው ላይ ራስ ካሣ ሲናገሩ፣ <u>" ... መቸም ደህና አድርገህ በተማርከውና ጥሩ አድርገህ በምትናገረው ቋንቋ ለመሟገት ዕድሉ ስለገጠመህ፣ ይህን ሁሉ ምርት መሰብሰብ ችለሃል፡፡</u> እንግዲህ! እነዚህ ያመጣኻቸው ሁሉ ለኢትዮጵያ ፍሬያማ እንዲሆኑ ከመመኘት በስተቀር፣ የምንጨምረው የለም ... " በማለት ቅኔ ያለበት ንግግር አድርገዋል፡፡ በእኔ በኩል ይህንን ንግግር በማስታወሻዬ ላይ ይገኔ ደጋግሜ ባነበውና ባጠናውም፣ ይልማን የሚነካው ቅኔ የት ላይ እንደሆነ እስካሁን አልገባኝም፡፡ (የራስ ካሣ ቅኔ የተባለውን አንዳንድ ሰዎች እንደተረጐሙልኝ፣ "የተማርከው እንግሊዝ፣ ቋንቋህ እንግሊዝ" ስለሆነ፣ ምንም አልተቸገርክም ለማለት ነው ይላሉ) ትልልቆቹ ሚኒስትሮች እነ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና አቶ መኰንን ሀብተወልድም ለይልማ የሥራ ፍሬ፣ መልካም አስተያየት መስጠታቸውን ሰምተናል፡፡ ለዚህ ሁሉ ፕሮሴቬርባሉን ብታገኝ ጥሩ ይሆን ነበር አሉኝ፡፡ ክቡር አቶ ምናሴ ለማ እንደመከሩኝ፣ አዲስ አበባ መጥቼ ይህንን ስለ ይልማ ሚሲዮን ውጤት ጉዳይ በቤተመንግሥቱ ስለተደረገው ስብሰባ የተያዘውን ዝርዝር ቃለ ጉባኤ ለማግኘት በጽሕፈት ሚኒስቴርና በልዩ ጽሕፈት ቤት ይሠሩ የነበሩትን የቀድሞ ሰዎች አነጋግሬ ለማግኘት ሞክሬ አለተሳካልኝም፡፡ ይልማ ሚሲዮኑን ሲቀበሉ የሚገልጸውን የመጀመሪያውን ቃለ ጉባኤ ያገኘሁት፣ በጸሐፊ ትዕዛዝ አክሊሉ ሰነዶች ውስጥ ነበር፡፡

የሆነ ሆኖ፣ የክቡር አቶ ይልማ ዴሬሣ የአሜሪካ ሚሲዮን እጅግ ፍሬያማ የሆነ ውጤት መያዙ የተረጋገጠ ነው፡፡

- በኢትዮጵያና በአሜሪካ መንግሥታት መካከል የተከፈተው የዲፕሎማቲክ ግንኙነት ሥራውን ጀምሮ ንጉሠ ነገሥቱ ተደስተዋል፡፡
- ኢትዮጵያ በፕሬዚዳንት ሩዝቬልት የሌንድ ሊዝ (Lend Lease) የእርዳታ ፕሮግራም ተጠቃሚ ለመሆን ችላለች፡፡
- ኢትዮጵያ የራሷ ገንዘብ (Currency) እንዲኖራት ተደርጐ፣ ከኢስት አፍሪካ ሽልንግ መገበያያና ከስተርሊንግ ዞን ነጻ መሆን ችላለች፡፡
- ጆርጅ ብላወርስ (George Blowers) የተባለው አሜሪካዊ፣ የእንግሊዝ ዜጋ በሆነው በሚስተር ኮሊዬ (Collier) ቦታ፣ የኢትዮጵያ መንግሥት ባንክ ገዥ ሆኖ ተሾሟል፡፡
- ሚስተር ጆን ስፔንሰር (John Spencer) የተባለው አሜሪካዊ፣ ከእንግሊዞች ጋር ለሚደረገው ውል ዝግጅት፣ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር የሕግ አማካሪ ሆኖ እንዲሠራ ተቀጥሯል፡፡